أمهـري

لغيـر المسلمـين

سلسلة الهداية (1)

# ስለ ኢስላም

## ምን ያህል ያውቃሉ?

## مـا هـو الإسـلام؟



# What is ISLAM?

ዓለም አቀፍ የባህል ጥናት ማዕከል

ኢራን

# ስለ ኢስላም ምን ያህል ያውቃሉ ?

ዓለም አቀፍ የባህል ጥናት ማዕከል

ኢራን



# ስለ ኢስላም ምን ያህል ያውቃሉ ?

በአሚር አባስ ዘማኒ

አልሁዳ አሳታሚ

ኢራን ፤ ቴህራን

ትርጉም፡- ወደ እንግሊዝኛ ቋንቋ

በዶ/ር ኤም ሐሺሚ

ከእንግሊዝኛ ቋንቋ ወደ አማርኛ

በአስማማው ዩሱፍ አብድልቃድር

አዲስ አባባ

ኢትዮጵያ

## በአላህ ስም እጅግ በጣም ርኅሩህ በጣም አዛኝ በሆነው ።

<u>*መቅድም*</u>

ይህ መጽሐፍ ኢስላምን ለማስተዋወቅ ወይም ኢስላምን ማወቅ ለሚፈልጉ ሁሉ በቀላል ሁኔታ የተዘጋጀ ነው ። ዓለም አቀፍ የባሕል ጥናት ማዕከል ሐይማኖትን በአግባቡ ማወቅ የባህል ግንኙነትን ያጠናክራል ከሚል በጎ መነሻና ጠንካራ አቋም አንፃር ያዘጋጀው ነው ። በመሆኑም በዓለም ዙሪያ ለሚገኙ አንባቢያን ኢስላምን ቀላልና ግልጽ በሆነ መንገድ የሚያስተዋውቀውን ይህን መጽሐፍ ስናዘጋጅ ለመንፈሳዊና ሞራላዊ እሴቶች መንገድ ከፋች እንደሚሆን በማመን ነው ።

ይህ መጽሐፍ ከሌሎች ሐይማኖት ተከታዮች ጋር፣የሚያስተሳስረንን፣የምንጋራቸውንና ልዩነት በሌሉን የእምነት ዓላማ ዙሪያ መቀራረብና ህያው ለሆነው ፈጣሪ ታማኝነታችን፣ በጎ አድራጊነታችን እና ጠቃሚነታችንን ለማረጋገጥ እንድንችል ታስቦ የተፃፈ ነው ።

ይህን መጽሐፍ ተጨባጭና እውን ላደረጉት ለዶ/ር አባስ ዛሚኒ እና ወ/ሮ ሰዲግሐህ ሻኩሪ ምስጋናችን የላቀ ነው ። ያለ እነሱ ድጋፍ ይህ መጽሐፍ በታሰበው መልኩ መዘጋጀት ባልቻለ ነበር ።

# ምዕራፍ 1

## ለሰው ልጆች የሐይማኖት አስፈላጊነት

### 1.1 መግቢያ

በዘመናችን የሰው ልጅ በሳይንስና ቴክኖሎጂ የመጠቀ ነው ። ሳይንስና ቴክኖሎጂን በመጠቀም ከፍተኛ ኤሌክትሮኒክስ መሳሪያዎችን አጋኘ በማድረግ በጣም ብዙ ነገሮችን አግኝቷል ። ከዚህ በተጨማሪ የኒዩክለር ሃይልን ለግልጋሎት ማዋል ችሏል። ተፈጥሮ በውስጧ ምንም ነገር መደበቅ እንደማትችል አድርጓታል ። በመሆኑም የዘመኑ የረቀቀ የሰው ልጅ የሳይንስና ቴክኖሎጂ ዕድገት የተፈጥሮን ዝምታ ሰብሮ ስፍር ቁጥር የሌላቸው ሚስጥሮችን ለማሳወቅ በቅቷል ። የ21ኛው ክፍለ ዘመን ሰው ወደር የለሽ ሊባል የሚችል የሳይንስና ቴክኖሎጂ ምጥቀት አሳይቷል ።

የሰው ልጅ ካለው ሰፊ እውቀትና ግንዛቤ አንፃር የተፈጥሮን ምስጢር ገላልጦ ለማሳወቅ ብሎም የተፈጥሮ ሃይሎችን በቁጥጥሩ ሥር ለማድረግ ያለው ፍላጎት ገና ጥያቄ ውስጥ ነው። በእርግጥ የሰው ልጅ ውድ በሆነ የራሱ ሥርዓት ሰራሽ በሆነው አስደሳች ዓለም በሰላም በመኖር ላይ ነውን ? በፈጠራቸው ታንኮችና በገነባቸው ውብ

ህንፃዎች የሳይንስና ቴክኖሎጂ ውጤቶች ረክቷል ማለት ይቻላልን ? በሌላ አነጋገር ‹‹ የሰው ልጅ ዓላማውን አሳክቷልን? ›› ለእውቀት፣ ለሥልጣን፣ በአጠቃላይ የከርሰምድርን ምስጢር ለመገላለጥና በጣም የተዋበ ቤተ-መንግስታት ለመገንባት ያለው ምኞት በእርግጥም የሕይወት አንድ ገጽታ ናቸው ። ነገር ግን ሌላው ገጽታው ሲታይ የሥልጣኔ ዕድገቱ፣ የቴክኖሎጂ ምጥቀቱና ሳይንሳዊ ምርምሩ የእርሱን ብቻ ሳይሆን የሌሎችን ፍጡራን ሕይወት ለአደጋ እየዳረገ ነው የሚገኘው ። የተክኖሎጂ ምጥቀቱ ገለልተኛ እንዲሆን ብሎም ራሱን ለቴክኖሎጂ መስዋዕት እንዲያደርግ አድርጎታል ። ማቋረጫ ለሌለው የምርትና ፍጆት አዙሪትና ለወደር የለሽ ጭካኔ አመቻችቶታል ።

ለዘመናት የሰው ልጅ ለሕይወቱ ጠቃሚ የሆኑ ቴክኖሎጂዎች ለማዘጋጀት ሲሞክርና ሲጥር ቆይቷል ። ቢሆንም ግን የፈጠራቸውን የቴክኖሎጂ ውጤቶች እንዲያመልክ ተገዷል። ለእነርሱም ሲል ሕይወቱን መስዋዕት እስከ ማድረግ ደርሷል ።

ለሰዎች የሚደረግ ክብር፣ ነፃነት፣ ፍቅርና ተስፋ ተሟጧል ። የሰው ልጅ ቅዱስ ህልውናውን ለቴክኖሎጂ ውጤቶች ለምን እንደሰጠ በራሱ ክብር ፣መብት፣ነፃነትና ፍቅር ፋንታ ለቴክኖሎጂ ውጤቶች ሰለባ እንደሆነ እያደር ሳያስገርመው አልቀረም ።

ዘመናዊ ሰው ለኑሮው የከፋ ፈተና አልገጠመውም። በሳይንስና ቴክኖሎጂ በመታገዝ መሰረታዊ የሆኑ የኑሮ ፈተናዎችን መቋቋም ችሏል ። ያም ሆኖ ግን መኖር ለምን አስፈለገ? ወይም ለምን እኖራለሁ የሚለውን መሰረታዊ ጥያቄ መመለስ ካልቻለ ዘመናዊ ሰው የሕይወት ጉዞውን አቅጣጫ መምረጥ አይቻለውም ።

## 1.2 ቁርአናዊ አመለካከት

ዓላማና አቅጣጫ የሌለውን ሕይወት ቅዱስ ቁርአን ትርጉም የለሽና ባዶ ሲል ይገልፀዋል ። ይህን መሰል የሕይወት አደጋ በተመለከተ እንዲህ ሲል ያስጠነቅቃል :-

« ቅርቢቱ ህይወት
ጨዋታና ዛዛታ፣ማጌጫም
በመካከላችሁም ፣መፎካከሪያ
በገንዘቦችና በልጆችም ብዛት
መበላለጫ ብቻ መሆንዋን
እወቁ ። (እርሷ) ቡቃያ ገበሬዎችን
እንደሚያስደስት' ዝናም ከዚያም
ቡቃያ እንደሚደርቅና ገርጥቶ
እንደምታየው ከዚያም የተሰባበረ
እንደሚኾን ብጤ ናት ፣
በመጨረሻይቱም ዓለም፣
ብርቱ ቅጣት ከአላህም
ምህረትና ውዴታ አለለ ፣የቅርቢቱም
ሕይወት የመታለያ ጥቅም እንጂ ሌላ
አይደለችም » (57፡20)

በሌላ ምሳሌ አላህ (ሱ.ወ) በቁርአን (24:39-40) የገነትና የመሬትን ብርሃን የዓለም ሁለንተናዊ እውነታን እንዲሁም የመጨረሻውን የሁለንተናዊ ዓለም በተመለከተ በግልጽ አስቀምጦታል ። በፈጣሪ ለማያምነው ሰለጠንኩ ባይ የሰው ልጅ ለአምላኩ ፍቅርና በእርሱም ላይ ተስፋ ቢስ ለሆነው የሰው ልጅ በሚያምር ሁኔታ አስቀምጦታል።

> ‹‹ እነዚህም የካዱት ሰዎች ሥራዎቻቸው (መልካሞቹ) በበረሃ ሜዳ እንዳለ ሲራብድ (አሸዋማ በረሃ ላይ በፀሃይ ሲያዩት የተንጋለለ ባህር መስሎ የሚታይ ነው ) የጠማው ሰው ውሃ ነው ብሎ እደሚያስበው በመጣም ጊዜ ምንም ነገር ኾኖ እንደማያገኘው ነው ። (ከሐዲው) አላህንም እስራው ዘንድ ያገኘዋል ። ምርመራውንም (ቅጣቱን) ይመለከታል ። አላህም ምርመራው ፈጣን ነው ።››
>
> 24:39)

ቁሳዊ ዓለም ያለ ሃይማኖት ባዶና በተሳያት እንደሚታይ የአስፋልት ላይ ውሃ መሰል ነገር ነው ። ወደ ቦታው በቀረቡ ቁጥር ከመጓጓት በቀር ጥምን ሊያረኩ የሚችሉበትን ምንም ዓይነት የውሃ ጠብታ እንደሌለው የበረሃ አሸዋ ነው ። አላማ ቢስ ራዕይና መጨረሻ የሌለው አመለካከት ነው ። በአጭሩ በጨለማ ውስጥ መዳከርና ጥቅጥቅ ባለ ጽልመት ውስጥ ሆኖ መደነቅ ብቻ ነው የሚሆነው ።

ከዚህ በተጨማሪ በማይመለሱ ጥያቄዎች ውስጥ እንዲዳክር ይሆናል።

«ሕይወት ምንድን ነው ?» የሕይወት የመጨረሻ አላማ ምንድን ነው ? ሳቅና ደስታ ለምንድን ነው ያስፈለገው? ከዚህ ሁሉ ጣጣ ማምለጫው መንገድ የቱ ነው ? የማምረት፣ የመብላት፣ የሥልጣን፣የተራክቦ፣የመፍጠን ዓለም ምክንያቱ ምንድን ነው ? የመጀመሪያ ተጓዥ ተንቀሳቃሽ የአሁኑ የተሽከርካሪ ዓይነትና ብዛት፤ በታንኮች ሌሎችም ዘመናዊ መኪናዎች ለምን ጉዞአቸውን ጀመሩ ? ለምንስ ዓላማ ተፈበረኩ፣ ወዴትስ እያመሩ ነው ? የትና ወደ የትኛው መዳረሻ እየተጓዙ ነው ? በሚሉ ምስቅልቅል ጥያቄዎች ይጨናነቃል ::

## 1.3 ዘመናዊው ሳይንስና የሰው ልጅ ፍላጎቶች

በሰውና በሌሎች ፍጡሮች መካከል ያለው መሰረታዊ ልዩነት የሰው ልጆች መሰረታዊ ከሆኑት ፍላጎቶች መካከል ከምግብና መጠለያ (ከነዚህ ውጪ) ፤ የሰው ልጅ ደህንነት /ነፃነት/ እና ችግር፤ ሃላፊነት ፣ጥያቄ የማንሳትና የመጨነቅ እንዲሁም በኑሮና በሞት መካከል ስላሉ ሁኔታዎች የማሰብና ንቁ የመሆንና የመሳሰሉት ጉዳዮች ላይ መጨነቁ ከሌሎች ፍጡሮች የተለየ ያደርገዋል ። እነዚህ ሁሉ ነገሮች የሰውን ልጅ ልዩና ታላቅ ፍጡር ቢያስብሉትም እነዚህ

ነገሮች በሌላ መልኩ መከራና ችግር ላይ ሲጥሉት ይስተዋላሉ ።

ይህን የሰው ልጅ የኑሮ ሁኔታ ባማረና ውብ በሆነ አገላለጽ ቁርአን እንዲህ ሲል አስቀምጦታል ።

« እኛ አደራን በሰማያትና በምድር
በተራራዎችም ላይ አቀረብናት፤
መሸከሟንም እምቢ አሉ ፤
ከርሷም ፈሩ ፤ ሰውም ተሸከማት፤
እርሱ በጣም በደለኛ ተሳሳች ነውና ፤ »

*(ቅ.ቁ 33:72)*

የሰው ልጅ በዚህ አያ /አንቀጽ/ እንደተገለጸው ከጌታው የተወረደለትን መለኮታዊ ሃላፊነት የመሸከም ግዴታው በርሱ (በሰው ልጅ) ላይ እንደሆነ ነው ። በሌላው የቅዱስ ቁርአን አንቀጽ እንደተቀመጠው ፤

« አዳምንም ስሞችን ሁሏንም አስተማረው ፤ከዚያም በመላዕክት ላይ (ተጠሪዎቹን) አቀረባቸው ፤እውነተኞችም እንደሆናችሁ የነዚህን (ተጠሪዎች) ስሞች ንገሩኝ አላቸው ። »

(ቅ.ቁ 2:30)

የሰው ልጅ ልዩ ፍጡር የሚያስብለው ለችግሮቹ መልስ ለመስጠት መጣሩ፤ ለሚያጋጥመው ችግርና ለብቸኝነቱ

እንዲሁም ለሚመጣበት በሽታና ሞት ምላሽ ለመስጠት ጥያቄዎችን ሲያነሳና ሲጥል መታየቱ ነው። የሰው ልጅ ወደዚች ዓለም ለምን መጣ (የአዳም ወደ ምድር መውረድ )? ለምን የሰው ልጅ ነጻ፤ ሃላፊነት የሚሰማውና የሚጨነቅ፤ ሆኖ ተፈጠረ ? ለምንስ የሰው ልጅ የተገደበ ሆነ ? ለምን የሰው ልጅ ይቸገራል ? ወዘተ . . . የእንዲህ ዓይነት ጥያቄዎችን መልስ ለመመለስ የሰው ልጅን አጠቃላይ አፈጣጠርና የመኖር ሂደት ማየት ግድ ይላል ። እነዚህንም ጥያቄዎች እንደ ነባራዊ የሰው ልጅ ጥያቄዎች ከሰው ልጆች ጋር አብሮ የተፈጠረ አድርጎ መቁጠር ይገባል ።በመሆኑም እነዚህ ጥያቄዎች ለቀድሞውም ሆነ ለአዲሱ ትውልድ ለአዛውንቱም ሆነ ለወጣቱ አዲስ አይደሉም ።

የጥያቄዎችን ወቅታዊነትና ጠቀሜታ በትክክል ከነባራዊ ሁኔታ አንፃር ጠቃሚነታቸውን በተመለከተ ከሥነ-ጽሑፍ ዕድገትና ፍልስፍና እንዲሁም ሥነ-ጥበብ አስተሳሰብ ጋር ያላቸውን ተያያዥነት ማንም ሊክደው አይችልም። የሁለንተናዊ ዓለም ጩኸትና ብሶት ሳያግዳቸው የሰው ልጆች አካባቢያቸውን በማጥናትና በመገንዘብ ረገድ በሚያደርጉት መስተጋብር ድብቅ የሆኑ ጥያቄዎችን አውቆ መልስ በመስጠት ረገድ ሙከራዎቻቸውን ቀጥለዋል ። ቢሆንም ግን ዘመናዊ ሰው አሁን በደረሰበት ቴክኖሎጂና ሳይንስ እንዲሁም የአስተዋይነት ደረጃ ጭምር የገጠሙትን

(የሚፈታተኑትን) ጥያቄዎች መመለስ አልቻለም። በዚህ ዘመን የሚገኘው የሰው ልጅ የተመቸውና ባለሙሉ ተስፋ በመሆኑ ከቀደምት አያቶቹ የተሻለ ነው ወይ ?

ይህን በተመለከተ የሚሠጠው አስተያየት የሚመለከተው የዘመኑ ሰው የገጠሙትን አለማዊ ፈተናዎች በአግባቡ ለይቶና አጢኖ መልስ ከመስጠት ይልቅ አጨቃጫቂነታቸው እንዲቀጥል አቅጣጫ በሌለው አካሄድ በመሄዱ ምክንያት ዛሬም ቢሆን መፍትሄ አላገኘላቸውም። በየጊዜው የሚገጥሙትን ችግሮች ሳይንስ መልስ እንደሚያዘጋጅላቸው እና ለዕለት ተዕለት ፍላጎታቸው መፍትሔ እንደሚያበጅላቸው ዓይነት አካሄድ የሚከተል ፍጡር ሆኗል ነው ፡፡

ሌላው የሰው ልጅ የሚከተለው መንገድና የኑሮ ፍልስፍና ለጨለምተኝነት አስተሳሰብ፣ የሞት ፍራቻ፣ ብቸኝነት፣ ሰቆቃ፣ ግለኝነትና ተስፋ መቁረጥን በተመለከተ ሳይንስ መልስ ይሰጥ ይሆን ? ከሚል አስተሳሰብ ነው። በርግጥ ሳይንስና ቴክኖሎጂ ለሰው ልጅ ሰላም ተስፋ እና ብልጽግና ሊያመጡ ይችላሉ ? የመሳሰሉትን ጥያቄዎች በማንሳት በዓለም ዙሪያ የሰው ልጅ ህልውና በተመለከተ የሚጋረጡትን ጥያቄዎች ከማስተንተን አልፎ ተግባራዊ ምላሽ ለመስጠት ይሞክራል ፡፡

አስፈሪው እውነታ ግን ለጥያቄዎች ሁሉ የሚገኘው መልስ ተቃራኒ መሆኑ ነው። የሰው ልጅ በጣም ጉጉ ከመሆኑ የተነሳ የ18ኛው ክፍለ ዘመን አዲስ ሳይንስ በተለይም ፊዚክስ እና የሥነ-ጹሁፍና ፍልስፍና ሥራዎች የሰው ልጅ የገጠሙትን ፈተናዎች ሁሉ በሳይንስ መሳሪያነት መልስ ያገኛል ብሎ ማሰቡ ነው ። ሆኖም ግን ባሰበው መንገድ ለገጠሙት ችግሮች ሁሉ መልስ ማግኘት ባለመቻሉ አጉል ተስፋውን ችላ በማለት ሳይንስና ቴክኖሎጂ ሁለንተናዊ ዓለምን ለማወቅና የተጋረጡትን ጥያቄዎች ሙሉ በሙሉ መመለስ እንደማይችል የተቀመሩት ዘዴዎችና የተዘጋጁት መሳሪያዎች ለአንዳንድ ሁኔታዎች መንገድ ከመፍጠር በቀር ሙሉ ምላሽ መስጠት እንደማይችሉ መገንዘብ ችሏል ። የሳይንስና ቴክኖሎጂ መገልገያ መሳሪያዎች ሙሉ አለመሆን ወይም ያለመሆን ለባለሙያዎቹ አነጋጋሪ ሆኖ ቀጥሏል ። በርትራንድ ሩሰል የተባለ ዘመናዊ ፈላስፋ ፣የሂሳብ ባለሙያ /አዋቂ/ እና የሎጂክ ሰው ስለ ዘመናዊ ሳይንስ ያለው አስተሳሰብ በጣም ቁጥብ ነው በሳይንስ ላይ ያለውን ውስንነት በተመለከተ ሲያስቀምጥ፣የሰው ልጅ በሳይንስና ቴክኖሎጂ ላይ ያለው የበላይነት በጣም ዝቅተኛ ነው። ሳይንስ ትርጉም የሌለው ዓለምን ያቀርብልናል /ያሳየናል/። በትክክል የዓለምን ምንነት እንፈልግ ዘንድ አያመቻችልንም። ለነዚህ ሁሉ ምክንያት

ራሱ ሰው ጭፍን ምክንያቶች ስላሉት ነው ። ስለዚህም ሩሴል እንዲህ ይላል ፦

‹‹ የሰው ልጆች ፤ዕድገታቸው፣ ተስፋቸው፣ ፍርሃታቸው፣ ፍቅራቸው፣ እምነታቸው የሚፈጠረው በአጋጣሚ ከአተሞች (atoms) ጋር በሚኖራቸው መስተጋብር ነው ።ማንም ፈላስፋ ሳይንቲስት በምንም ዓይነት ማነቃቂያም ሆነ ማበረታቻ ምክንያት በሚያደርገው ተግባር ሰውን እንደ ሰው ህያው አድርጎ ሊያቆይ አይችልም። የሰው ልጆች ጥረት ሁሉ ለዘመናት የፈጠሯቸው እና የፈለሰፏቸው መስዋዕትነት የከፈሉባቸው ታላላቅ ነገሮች ሁሉ ጠቅላላ የዓለም ሥርዓት ሲያበቃ ከመውደም በቀር ቀጣይ ሊሆኑ አይችሉም ። ››

ከዚህ ማሳሰቢያ አንጻር ስንመለከተው የተስፋ መቁረጥ ሁኔታዎች ብቸኝነትና ስቃይ የአለማዊ ህይወት መገለጫዎች ናቸው ። ለዚህ ነው ቅዱስ ቁርአን ህይወትን በተመለከተና ኢ.አማኒያን የሚፈጽሟቸውን ተግባሮች እንደሚከተለው ያስቀመጠው ።

> ‹‹ እነዚያም የካዱት ሰዎች ሥራዎቻቸው (መልካሞቹ) በበረሃ ሜዳ እንዳለ ሲራብድ የጠማው ሰው ውሃ ነው ብሎ እንደሚያስበው፤ በመጣውም ጊዜ ምንም ነገር

ሆኖ እንደማያገኘው ነው፤ (ከሃዲው) አላህንም
እሥራው ዘንድ ያገኘዋል፤ ምርመራውንም
(ቅጣቱን) ይመለከታል አላህም፣ምርመራው
ፈጣን ነው . . . ››

(ቅ.ቁ 24፡39)

ወይንም ደግሞ በዚህ መልክ አስቀምጦታል ።

‹‹ ወይም (መጥፎ ስራዎቻቸው) ከበላዩ
ማዕበል ፤ከበላዩ ደመና፤ ያለበት ማዕበል
በሚሸፈነው ጥቅል ባህር ውስጥ፤እንዳሉ
ጨለማዎች ነው፤ (እነዚያ) ከፊላቸው ከከፊሉ
በላይ ድርብርብ የሆኑ ጨለማዎች ናቸው፤
(በዚህች የተሞከረ ሰው) እጁን ባወጣ
ጊዜ ሊያያት አይቀርብም፤ አላህም ለርሱ
ብርሃንን ያላደረገለት ሰው ለርሱ
ምንም ብርሃን የለውም ። ››

(ቅ.ቁ 25፡40)

ወይም ደግሞ

‹‹ ቅርቢቱ ህይወት፣ጨዋታና ዛዛታ፣
ማጌጫም፤በመካከላችሁም መፎካከሪያ
በገንዘቦችና በልጆችም ብዛት መበላለጫ
ብቻ መሆኗን ዕወቁ፤(እርሷ) ቡቃያ

ገበሬዎችን እንደሚያስደስት ዝናም ከዚያም
ቡቃያ እንደሚደርቅና ገርጥቶ
እንደምታየው ከዚያም የተሰባበረ
እንደሚሆን ቢጤ ናት፤ በመጨረሻይቱም
ዓለም ብርቱ ቅጣት ከአላህም ምህረትና
ውዴታ አለ ፤የቅርቢቱም ህይወት የመታለያ
ጥቅም እንጂ ሌላ አይደለችም ። ››
(ቅ.ቁ 57፡20)

## 1.4 *ስለ ህይወት ሁለት አመለካከቶች*

ሁለት የተለያዩ የህይወት አመለካከቶች አሉ ። እነርሱም ቁስ አካላዊያንና መንፈሳዊ ይባላሉ ።

እንደ ቁስአካላዊያን አመለካከት /ዕይታ/ አለም ባጋጣሚ የተገኘችና ምንም ዓይነት አላማና ግብ የሌላት ሲሆን በምንምና በማንም የበላይ ሃይል /መለኮታዊ ሃይል/ የምትመራ አይደለችም ብለው ያምናሉ። ሌላው የቁስአላካዊያን አመለካከት /ዕይታ/ ይህች ዓለም ምንም አይደለችም ድንገታዊ ክስተት እንጂ፤ በመሆኑም የሰው ልጅ ለዚህ ጊዜ ለወለደው ክስተት /ለውጥ/ ብቸኛው ተወቃሽ ነው ይላሉ ።

በሌላ በኩል እንደ መንፈሳዊያን አመለካከት (ዕይታ) የሰው ልጆችና የዚህ ዓለም መፈጠር ወይም ክስተት የራሱ የሆነ ዓላማና ግብ አለው ።

መኖር /መገኘት/ በአካላዊና ቁስአዊ ሁኔታዎች ብቻ የሚገለጽ አይደለም። በሰው ልጆች የስሜት ህዋሳት ሊዳሰሱና ሊታዩ ወይም ሊቀመሱ የማይችሉ ብዙ ነገሮች በመለኮታዊ ጥበብ በዓለም ውስጥ ሊገኙ እንደሚችሉ የማይታበል ሃቅ ነው ይላሉ ። መንፈሳዊያን ይህን የላቀ የፈጣሪ ጥበብ ከፍተኛ ግምት በመስጠት በራሳቸው ተፈጥሮአዊ ችሎታ ሊያውቋቸው የማይችሉ ፍጡራን እንዳሉ ያምናሉ ።

ቁሳአካላዊያን እና መንፈሳዊያን ከአመለካከታቸው አንጻር የሚለያዩባቸው ዋና ነጥቦች የሚከተሉት ናቸው ።

| ተ.ቁ | የቁሳአካላዊያን አመለካከት | ተ.ቁ | የመንፈሳዊያን አመለካከት |
|---|---|---|---|
| 1 | ዓለም የአጋጣሚ ግኝት እንጂ አፈጣጠሯ አላማ የለውም ። | 1 ,, , | የዓለም አፈጣጠር በፈጣሪ ዕቅድና ፍላጎት በምክንያት የተፈጠረ ነው። |
| 2 | ዓለም በህዋሳታችን አማካኝነት የምንገነዘባቸው ነገሮች ውጤት ነች። | 2 | ለእኛ ግልጽ ያልሆኑና ግልጽ የሆኑ ነገሮች በዚህ ዓለም ይገኛሉ ። ዓለም የሁለቱ ውጤት |

| | | | |
|---|---|---|---|
| | | | ነች ። |
| 3 | ተጨባጭ ዓለም እንጂ<br>የወዲያኛው ዓለም ተብሎ<br>የሚጠራ የለም ። | 3 | ከምድራዊ ዓለም<br>ሌላ ዘለዓለማዊ<br>ዓለም አለ ። |
| 4 | ይህች ዓለም<br>በድንገት የተገኘች<br>አላሚ ቢስ የሆነች<br>ሥርዓትና ደንቧ<br>ያልተሟላ ነች ። | 4 | ይህች ዓለም<br>በመለኮታዊ ሥልጣን<br>ሥር ያለች ስትሆን<br>ህልው የሆነና<br>ሥርዓት ያለው ሂደት<br>ያላት ነች ። |
| 5 | የሰው ልጅ እንደ ዓለም<br>አፈጣጠር ሁሉ በድንገት<br>የተገኘ በዓለም ላይ የሚኖር<br>ሲሆን ከሌሎች እንስሳት<br>በተሻለ መልኩ<br>የተፈጥሮ ህግጋትን<br>ተቆጣጥሮ የሚኖር ነው ። | 5 | የሰው ልጅ በምድር<br>ላይ የፈጣሪን<br>ግዴታ ለማሟላት<br>ወይም ለመፈፀም<br>የሚኖር ነው ። |

## *1.5 በዕምነትና በክህደት መካከል ያለ ወሰን*

በቅዱስ ቁርአን ውስጥ ባማረና ልዩ በሆነ ሁኔታ ቀደም ብለው የተጠቀሱ አይታዎችን /ምልከታዎችን/ ሲያብራራ፤

« ይህ መጽሐፍ ከአላህ ለመሆኑ ጥርጥር የለበትም፤ ለፈራህያን መሪ ነው ።
ለነዚያ በሩቅ ነገር የሚያምኑ ሰላትንም ደንቡን ጠብቀው የሚሰግዱ ከሰጠናቸውም ሲሳይ የሚቸሩ ለሆኑት ፤ »
(ቅ.ቁ 2፡2-3)

እነዚህ ቅደም ተከተላቸውን የጠበቁት የቁርአን አንቀጾች በአማኞችና ኢ-አማኞች መካከል ያለውን ልዩነት የሚያስገነዝቡና የሚገልጹ ሲሆን ፤በሁለቱ መካከል ያለው መሰረታዊ ልዩነት ከዕውነታቸው አንጻር ሲታይ አማኞች በማይታየው ነገር የሚያምኑ ሲሆን ኢአማኞች ደግሞ ይህን አለመቀበላቸው ነው ። እንደ ቁርአን እይታ ከሆነ በአላህ ማመን ሁሉንም ነገር ትርጉም እንዲኖረው ያደርጋል ።

« ሰፋና መርዋ ከአላህ (ትዕዛዝ መፈጸሚያ) ምክንያቶች ናቸው፤ቤቱን (ከዕባን)

በሐጅ ወይም በዑምራህ ሥራ የጎበኘ ሰው በሁለቱ (መካከል) በመመላለሱ በርሱ ላይ ሐጢአት የለበትም፤መልካምን ሥራ በፈቃደኝነት የሠራ ሰው (አላህ ይረዳዋል) አላህ አመስጋኝን አዋቂ ነውና።

(ቅ.ቁ 2፡156)

‹‹ አላህ የሰማያትና የምድር አብሪ ነው፤የብርሃኑ ምሳሌ በውስጧ መብራት እንዳለባት (ዝግ) መስኮት መብራቱ በብርጭቆ ውስጥ የሆነ፤ ብርጭቆይቱ ፍፁም ሉላዊ ኮከብ የምትመስል ምስራቃዊም ምዕራባዊም ካልሆነች ከተባረከች የወይራ ዛፍ፤ዘይቷ እሳት ባይነካውም እንኳ ሊያበራ የሚቀርብ ከሆነች (ዘይት) የሚቃጠል እንደሆነ (መብራት) ነው፤ ይህ በብርሃን ላይ የሆነ ብርሃን ነው፤ አላህ ወደ ብርሃኑ የሚሻውን ሰው ይመራል፤አላህ በነገሩ ሁሉ አዋቂ ነው። ››

(ቅ.ቁ 24፡35)

‹‹ ሰማያትና ምድርንም ሁሉ በሁለቱ መካከል ያለውንም ሁሉ ቀላጆች ኾነን አልፈጠርንም ። ሁለቱንም በምር

እንጂ አልፈጠርናቸውም፤ ግን
አብዛኛዎቻቸው አያውቁም ። ››

(ቅ.ቁ 44፡38-39)

‹‹ በሰማያት ያለውና በምድር ያለውም
ሁሉ የአላህ ነው ። ነገሮችም ሁሉ
ወደ አላህ ብቻ ይመለሳሉ ። ››

(ቅ.ቁ 3፡109)

‹‹ አንተ ሰው ሆይ አንተ ጌታህን (በሞት)
እስከምትገናኝ ድረስ ልፋትን ለፊ ነህ
ተገናኘውም ነህ ። ››

(ቅ.ቁ 86፡3)

እነዚህ የቁርአን ጥቅሶች እንደሚያመለክቱት አላህ (ሱ.ወ) የዓለማት ጌታ መሆኑን ሲሆን ፍጡራን ሁሉ በእሱ ፍላጎት በዓላማ የተፈጠሩ መሆናቸውን ማረጋገጥ ይቻላል። ምክኒያት፣ትርጉምና ብርሃን ዓለም በአላህ (ሱ.ወ) ላይ አሃዳዊ እምነት ያለው አማኝ በአግባቡ የሚገነዘባቸው

ክስተቶች ናቸው። በመሆኑም እምነት ስንል በሚታየውና በማይታየው ዓለም መኖር ማመንን ማረጋገጥ ሲሆን፤የሰው ልጅ መረዳት ከሚችለው በላይ ያሉ ነገሮችንም ፈጣሪ በቅዱስ ቁርአን በነገረው መሰረት ስለትክክለኛነታቸው ማረጋገጥ ጭምር ነው ። በዚህች ዓለም ስንኖር እንደ ሰው ማድረግ የሚኖርብን ነገር በተጨማሪ ሊጠቀሱ የሚገባቸው በመጽሐፍት ማመን በነብዩች ማመን፤በመላዕክቶች ማመን በመጨረሻ ቀንም (ምፅአት) ማመን፣በመለኮታዊ እርዳታ ማመን ናቸው ።

ይህች ዓለም የአጋጣሚ ሁኔታዎች ክስተት ናት ብለው ለሚያምኑ ቁስአካላዊያን አመለካከት ቅዱስ ቁርአን የእነርሱን ዓለማቢስነት ፣ባዶነት፣ሞራል አልባነት ማስረጃ በመጥቀስ ሃሳባቸውን አምላኪ ሐጥአን መሆናቸውን በተጨባጭ ያረጋግጣል ።

« እርሷም (ሕይወት) የቅርቢቱ
ሕይወታችን እንጂ ሌላ አይደለችም።
እንሞታለን፣ሕያውም እንሆናለን ፡፤
ከጊዜም(ማለፍ) በስተቀር ሌላ አያጠፋንም
አሉ። ለነርሱ በዚህ (በሚሉት) ምንም
ዕውቀት የላቸውም እነርሱ የሚጠራጠሩ
እንጂ ሌላ አይደሉም ። »

(ቅ.ቁ 45:24)

ዓለም ተጨባጭ እና ገሃድ ዓለም ብቻ ነች ብለው ለሚያምኑ ቁስአካላዊያን ሞትና ህይወት የተፈጥሮ ክስተት ብቻ ናቸው ፡፡ በአንድ ወቅት መኖር በሌላ ጊዜ ቅርጽን ለውጦ ቁስ ሆኖ መኖር እንጂ ፈጣሪም ጠያቂም አምላክ የለም ይላሉ ፡፡ በመሆኑም ግባቸው በገሃዱ ዓለም ተደስተው መኖር ብቻ ነው ፡፡

የማይታየውን ዓለም (ዘለዓለማዊ የሆነውን ዓለም) ያረጋገጠ ሳይንስ ባለመኖሩ ከሞት በኃላ ለሚኖረው ሕይወት ደንታ የላቸውም ሞትና ሕይወት በዓለም ሕግጋት ሥር ናቸው ካሉ ሊገነዘቡ የሚገባቸው ነገር እንዳለ በፍጹም አላጤኑትም ፡፡ እነርሱ የፈጠሩት ሳይንስ ሊደርስበት ካልቻለ የፈጠራቸውን አምላክ ማጣጣል ይገባቸዋል ወይ? ዘላለማዊ ዓለም ከገሃዱ ዓለም የተለየ ዓለም መሆኑን ማወቅ ይገባል ፡፡ ሁሉንም የፈጠረ የዓለማት ጌታ አላህ (ሱ.ወ) የሰው ልጆችንም የሚሰሩትን የፈጠረ ነው፡፡ ሙሉ እምነታቸውን በሳይንስ ላይ ያደረጉ ዓለማዊያን የሳይንስ መሳሪያዎች ውጤታማ አለመሆንና ሳይንሳዊ ዘዴዎችም የተፈጥሮ ህግና ሥርዓትን ምልከታ ለማድረግ ብቃት የሌላቸው ሆነው አግኝተዋቸዋል ፡፡ በመሆኑም ሳይንስ አምንታዊ ወይም አሉታዊ አስተያየት ወይም ፍርድ በተፈጥሮ እውነት ላይ ማለትም ቁሳዊ ባልሆነ ሕይወት ላይ መዳኘት አይቻለውም፡፡

## *1.5 የሕይወት መኖር ደረጃዎች*

የሕይወት መኖር ደረጃዎችን በተመለከተ ሁለት መሰረተ ጉዳዮች ትኩረት ይሰጣቸዋል ። ከኢስላም ሌላ የመጽሐፍት ሰዎች ተብለው የሚጠሩ የሚከተሉት ሃይማኖትም እንዲሁ በሁለት ዐብይ ነጥቦች ላይ ይስማማል ። አንደኛው የሚነካውና የሚለካው ቁሳዊ ዓለም ሲሆን ደረጃው ዝቅተኛ ነው ። ከፍተኛው (የበለጠው) ዓለም ተብሎ የሚታወቀው ደግሞ ገሃድ ያልሆነው የማይታየው ዓለም ነው ። ይህ ዓለም ገይብ ተብሎ ይጠራል ። በዚህ በማይታየው ዓለም መላዕክት (መላይካዎች) ና አሚሮች (ዓለም ኢአምር) ይገኛሉ ።

በዚህ በከፍተኛው ዓለም ፈጣሪያችን አላህ (ሱ.ወ) አስማዕ-ወስ-ሲፋት (የአላህ ስሞችና ባህሪያት አንድነት) ፤መላዕክት፣ወህይ (ትዕዛዙን የሚገልጽበት) ይገኛሉ ። ይህ ከከፍተኛ ወደ ዝቅተኛ አቀማመጥ ደረጃ ሲታይ ነው ። ፈጣሪ ፍጹም ዘለዓለማዊ ነው ለፈጠራቸው ዓለማት ሁሉ ዓላማ አለው ። ምክኒያት አለው ። ለአላህ የፍጡሮች ባህሪያትን መስጠት አይቻልም ። እነዚህን የተውሂድ መስፈርቶች በተመለከተ ቅዱስ ቀርአን እንዲህ ይላል ፡-

« አላህም ከእናቶቻችሁ ሆዶች

ምንም የማታውቁ ሆናችሁ

አወጣችሁ፣ታመሰግኑም ዘንድ
ለናንተ መስሚያን ማያዎችንም
ልቦችንም አደረገላችሁ ። ››

(ቅ.ቁ 16፡78)

‹‹ ከዚያም (ቅርጹን) አስተካከለው
በርሱ ውስጥም ከመንፈሱ ነፋበት
(ነፍስ ዘራበት) ለናንተም ጆሮዎች
ዓይኖችና ልቦችንም አደረገላችሁ ።
በጣም ጥቂትን ብቻ ታመሰግናላችሁ።››
(ቅ.ቁ 32፡9)

አንድ ሰው የተሰጠውን አካል (ልብ) በአግባቡ የማይጠቀምበት ከሆነ ቁርአን እንሰሳ ይለዋል ።

‹‹ ከጋኔንም ከሰዎችም ብዙዎችን
ለገሃነም በእርግጥ ፈጠርን። ለነርሱ
በራሳቸው የማያቁባቸው ልቦች አሏቸው ።
ለነሱም በራሳቸው የማያዩባቸው ዓይኖች
አሏቸው ። ለነሱም በራሳቸው
የማይሰሙባቸው ጆሮዎች አሏቸው ። እነዚያ
እንደ እንሰሳዎች ናቸው። ይልቁንም እነርሱ

በጣም የተሳሳቱ ናቸው ። እነዚያ ዘንጊዎቹ
እነርሱ ናቸው ።

(ቅ.ቁ 7፡179)

እንደተመለከትነው ቁርአን ልብን የሰው ልጅ የማሰቢያና የማመዛዘኛ የአካል ክፍል እንደሆነ አድርጎ ይቆጥራል ። የሰው ልጆች አካባቢያቸውን እንዲያስተውሉ ፣ እንዲያጠኑና ከሚያዩትና ከሚጨብጡት ነገር በስተጀርባ ያለውን ሌላውን የማይታይ ዓለም በዐይነ ህሊናቸው እንዲቃኙት ቅዱስ ቁርአን ይጠይቃል ። ያበረታታል ። እንዲህ በማድረግ ብቻ ነው የሰው ልጅ እውነታውን ሊያውቅ የሚችለው ። ይህን በተመለከተ ቅዱስ ቁርአን በተለያዩ ሁኔታዎች የተለያዩ ጉዳዮችን በመጥቀስ እውነታውን አንፀባርቋል። ተፈጥሮን በተመለከተ ሲገልጽ ፤

‹‹ የሰማያትና የምድር ንግሥና ለአላህ
ብቻ ነው አላህም በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው
። ሰማያትና ምድርን በመፍጠር ሌሊትና ቀን
በተመለከተ ለባለ አእምሮዎች በእርግጥ
ምልክቶች አሉ ። ››

(ቅ.ቁ 3፡189-190)

ቅዱስ ቁርአን ታሪክን መሰረት በማድረግ ሲያብራራ ፡-

‹‹ በሻንም ኖሮ በርሷ ከፍ ባደረግነው
ነበር። እርሱ ግን ወደ ምድር ተዘነበለ።
ፍላጎቱንም ተከተለ። ብጤውም ብታባርረው
ምላሱን አውጥቶ የሚያለኽልህ ወይም
ብትተወው ምላሱን አውጥቶ የሚያለኽልህ
እንደ ኾነ ውሻ ነው ። ይህ የዚያ
በአንቀጾቻችን ያስተባበሉት ሕዝቦች ምሳሌ
ነው ። ያስተነትኑትም ዘንድ ታሪኮች
ተርክላቸው ። ››

(ቅ.ቁ 7፡176)

ወህይን (የአላህን ትዕዛዝ) በሚመለከት ቁርአንን አያስተነትኑም! አያጤኑም ወይ! የአላህ (ሱ.ወ) ቃል ልባቸውን አትሞታልን ?

‹‹ ቁርአንን አያስተነትኑምን ?
በውነቱ በልቦቻቸው ላይ
ቁልፎቿ አልሉባትን ?

(ቅ.ቁ 44፡24)

ሰዎች እውነትን ፍለጋ እንዲያተኩሩ እንዲመራመሩ በአጠቃላይ የዓለምን ሁኔታ በአግባቡ እንዲረዱ ቁርአን ትክክለኛ አቅጣጫን ለሰው ልጆች የሚያመላክት ከመሆኑም

በላይ ትርጉም የለሽና አቅጣጫ ቢስ የሆነውን ሕይወታቸውን ትርጉም ወደአለው ጣፋጭ ሕይወት ይመራቸዋል ፡፡

# ክፍል 2

## ኢስላም ምንድን ነው ? ኢስላም ምን ማለት ነው ?

### 2.1 በዘመናችን ኢስላምን ማወቅ ወይም ማጥናት ለምን ይጠቅማል? (ፋይዳው ምንድን ነው)

ኢስላም የነቁና ያወቁ የሰው ልጆች አእምሮ የሚያስተናግደው እውነተኛ ሐይማኖት ነው ፡፡ ከሁለቱ መለኮታዊ ሐይማኖቶች ከጁዳይዝምና (የአይሁዶች እምነት) ክርስትና ጎን ለጎን ከፍተኛ ክብርና ዝና ያተረፈ እምነት ነው፡፡ በየቀኑ በጣም ብዙ በመቶዎች የሚቆጠሩ መጽሐፍት፣መፅሔት፣ መጣጥፍ ሌክቸሮች እስላምን በተመለከተ ይፃፋሉ፤ ይነገራሉ፤ ውይይት ይደረግባቸዋል ፡፡ የኢስላም ምንነትና ክብር በዘመናችን እያደገ የመጣ ከመሆኑም ባሻገር ፣ ለነፃነት፣ ለምክንያታዊነት፣ ለስልጣኔና ለመሰል ሁኔታዎች መፍትሔና መጠቀሚያ ቁልፍ ሆኖ

ተገኝቷል ። በተለይም ደግሞ የትኩረት ማዕከል እየሆነ የመጣባቸው ሁኔታዎች በእነዚህ ምክንያቶች ነው።

- የ6ቱ ቀን የአረብ እስራኤል ጦርነት
- በቦስኒያ በኦርቶዶክስ ሰርቦች የተገደሉ ሙስሊሞች
- በኢራን የተካሄደው ኢስላማዊ አብዮት እና የፈጠረው አዲስ የዓለም ህዳሳዊ ማዕበል ።
- ኢስላምና የምዕራቡ ዓለም ግጭት
- የኮሚኒኬሽን ስርዓት ማደግና ግሎባላይዜሽን መፈጠር ።
- በሐይማኖት ምሁራንና በባለሥልጣኖች መካከል የሚካሄዱ ውይይቶች።

እነዚህ ሁኔታዎችና ሌሎች በየጊዜው የሚከሰቱ ሁኔታዎች የሰው ልጅ ሃቅን እንዲፈልግ እውነትን እንዲከተል ተፅዕኖ በመፍጠራቸውና በማስገደዳቸው ወደ ሐይማኖት እንዲያዘነብል እንዲመራመር በር ከፍተዋል ። በመሆኑም የሰው ልጆች ከተጋረጠባቸው ችግሮች ለመውጣት ብቸኛው አማራጭ ኢስላም ሆኖ አግኝተውታል ።

የመለኮታዊ አንድት ፣መለኮታዊ መልዕክትን ይዘት በመረመሩ ቁጥር ኢስላም የሕይወት ቁልፍ የዓለም መመሪያና የዘለዓለም ሕይወት መሥመር መሆኑን

ሊያረጋግጡ ችለዋል ። የኢስላም መልዕክት በዓለም ውስጥ ለነፃነታቸው ለሚታገሉ፣በድህነት አዘቅት ውስጥ ላሉ በሚሊዮን ለሚቆጠሩ ጭቁኖች የክብርና የነፃነታቸውን መንገድ እንዲፈለጉ አነቃቅቷቸዋል ።

ኢስላም ዛሬ በመላው ዓለም በተለያየ ባህልና አስተሳሰብ ባላቸው ህዝቦች የሚዘወተር ተቀባይነት ያለውና ለችግራቸው ምላሽ ሰጪ ሐይማኖት ነው። ዘር ፣ቀለምና መልካምድራዊ ሁኔታ ሳይበግረው በአፍሪካ ፣በኢስያ፣ በደቡብና ማዕከላዊ አሜሪካ እስከ ቻይናና የሕንድ ክፍለ ዓለም ድረስ ተስፋፍቶ ይገኛል ።

የአረቢኛ ቋንቋ ይዘትና ጣዕመ ልሳን ከምክንያታዊ ቋንቋነት አንጻር ኢስላም ከዓለም ጫፍ እስከ ጫፍ እንዲስፋፋ አስችሎታል ።

ኢስላም ለምን ሊስፋፋ ቻለ ? ኢስላም እንደ ኃይማኖት ተቀባይነት አግኝቶ መስፋፋት የቻለው ከቢሊዮን ህዝብ በላይ አማኞች ስላሉት ብቻ አይደለም። ዋናው ቁምገር ግን የሙስሊሙ ስልጣኔ የአውሮፓንና የአሜሪካንን ስልጣኔዎች በማምጣት ረገድ የተጫወተው ሚና ችላ የማይባል በመሆኑ ነው ። በአሁኑ ወቅት ኢስላም በአውሮፓ ትልቁ ሁለተኛው ሐይማኖት ነው። በአሜሪካም ቢሆን ከአይሁዳዊው ቁጥር የሙስሊሙ ብዛት ይበልጣል። ኢስላምን ለማጥናት የምንገደድበት መሰረታዊ ጉዳይ ግን

ከአማኞች ብዛትና ስርጭት ብቻ ሳይሆን ኢስላም መለኮታዊ ሃይማኖት በመሆኑ መለኮታዊ መልዕክቱ ለሰው ልጆች ወደር የለሽ ፋይዳ ስላለው ነው ። ኢስላም መለኮታዊ ከሆኑት ሐይማኖቶች አንዱና ማጠናቀቂያ ሐይማኖት ነው። አላህ (ሱ.ወ) ካወረዳቸው ቅዱስ መድሐፍት ውስጥ የአላህን (የፈጣሪን) አንድነት በመጠበቅ ረገድ ከነቢዩላህ ኢብራሂም (አብርሃም) (ዐ.ሰ) እስከ ነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ያለውን የእምነት መሰረት በአላህ ስሞችና ባህሪያት አንድነት (ተውሂድ አል-አስማእ ወሰ-ሲፋት) ላይ የጠነከረ አቋም ያለው ሃይማኖት ነው ። ጁዳይዝም እና ክርስትናን ለማጥናት የሚፈለግ ማንም ተመራማሪ ኢስላምን ሳያውቅና ሳያጠና የሚያደርገው ሙከራ ሁሉ ዉጤት አይኖረውም።

## 2.2 ማጠቃለያው ሐይማኖት እና መደምደሚያው ነብይ

ኢስላም የመለኮታዊ ሐይማኖት ማጠቃለያ ሲሆን ነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የነብዮች ሁሉ ቁንጮና መደምደሚያ ናቸው ። "ኸተመል አንቢያእ" የነብያት ሁሉ መቋጫ በማለት አላህ በቅዱስ ቁርአን ያወድሳቸዋል ።

የታሪክ ፀሃፊያን ነብዩ መሐመድን (ሰ.ዐ.ወ) በሐይማኖት ታሪክ ውስጥ የሰውን ልጅ ሥነ-ልቦናና ማህበራዊ ሕይወት በከፍተኛ ደረጃ መለወጥ የቻሉ ታላቅ

የሐይማኖት መሪ በማለት ያወድሷቸዋል ። በተለያዩ ጊዜያት የተለያዩ ሃይማኖቶች ተከስተዋል ። በተለይ በሕንድ በጣም ብዙ ሐይማኖትና የሐይማኖት መሪዎች ሕዝቡን ለማንቀሳቀስና የሐይማኖታቸው ተከታይ ለማድረግ ጥረዋል ። ነገር ግን ከስኬት አንፃር ስንመዝነው ነብዩ መሐመድን (ሰ.ዐ.ወ) የሚያክል የሐይማኖት መሪ አልታየም በማለት የታሪክ ፀሐፊያን ይመሰክራሉ ።

ከነብዩ አደም (ዐ.ሰ) የመጀመሪያው የሰው ልጆች አባትና ነብይ በመቀጠልና በመያያዝ ከመጡት እምነቶች መደምሚያው ሐይማኖት ኢስላም ነው ። በእስልምና ሐይማኖት ተውሂድ የኢስላም መሰረት መሆኑና በትክክል የሚገልፀውም ‹‹ ላኢላህ ኢልለላህ›› (ከአላህ በስተቀር ሌላ አምላክ የለም) የሚል ሀረግ ነው ። ይህ በአንድ አምላክ የማመን ሁኔታ በቀደምት ሐይማኖቶችም የነበረ ቢሆንም፤ ለመጨረሻ ጊዜ መለኮታዊ አስተምህሮት የተገለጠው ለነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ነው ። እኒህ የነብዩች ማጠቃለያና ቁንጮ የሆኑት ነብይ እምነት ላይ አዎንታዊ ተፅእኖ በመፍጠር ከጥንት ጀምሮ የነበረውን በፈጣሪ አንድነት ማመን እንደ አዲስ አስተምረዋል ። አንድ ብቸኛና እውነተኛ ጌታ መኖሩን አምልኮም ተገቢ የሚሆነው ለርሱ ብቻ መሆኑን አረጋግጠዋል ። ያለፉት ነብዮች ሁሉ ያስተማሩት ስለ አላህ አንድነት መሆኑን አስገንዝበዋል ።

በኢስላም አመለካከት እምነት ከሰው ልጆች ሕይወት ጋር መኖር አለበት። ከሰው ልጆች ተፈጥሮአዊ ሁኔታ ጋር የተጣመረ ሲሆን የሰው ልጆችን ለማርካት የሚቻለውም በእምነት መሆኑን ያምናል ። የተፈጠርንበትን ዓላማ በተሟላ መልኩ ማወቅ ከሰው ተፈጥሮ ውጪ በመሆኑ ወሰን የለሽ የሆነውን የፈጣሪን ድርጊቶች ሙሉ በሙሉ ለማወቅ ባይችልም እሱን (አላህን) እንዲገዛ የፈጠረው ስለሆነ ከዚህ ዓላማ አንፃር ፈጣሪውን እስከ ሕይወት መጨረሻ ሲገዛ ይኖራል። ከዚህ ውጭ ግን ሐይማኖትን ለመዝናኛ ፣ለይስሙላ ፣ወይም እንደ ባህል ለሚቆጥሩት አስጠንቅቋቸዋል ።

‹‹ ጋኔንና ሰውንም ሊገዙኝ እንጂ
ለሌላ አልፈጠርኳቸውም ። ››
(ሱረቱል- ዛሪያት 51፤56)

እያንዳንዱ ሰው በእምነቱ ተጠያቂ እንደሆነና በፍርዱ ቀን ምንም ዓይነት ማስተባበያና ይቅርታ ተቀባይነት የሌለው መሆኑን ያስገነዝነባል ። አዳምን ሲፈጥር ሁሉም የሰው ልጆች በእርሱ ጌትነት ስላመኑና ቃል ኪዳንም ስለገቡ ይሕ ቃል ኪዳን በሰው ሩህ ላይ ታትሟል ። የሰው ጽንስ በእናት ማህፀን ውስጥ እያለ በአምስተኛ ወሩ ሩህ(ነፍስ) ወደ ፅንሱ ከመግባቱ በፊት እንኳን በሩህ ላይ ቀደም ብሎ ይህ

ቃልኪዳን ታትሟል። ስለዚህ ህፃኑ ሲወለድ የተፈጥሮ እምነት (በአላህ እምነት) ይዞ ይወለዳል ። ይህ ተፈጥሮአዊ እምነት በአረበኛ *ፊጥራ* ይባላል። የተወለደው ሕፃን ብቻውን ማደግ ቢችል ኖሮ ስለ አላህና ስለ አንድነቱ ያውቅ ነበር ። ግን ሁሉም ህፃናት በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ አካባቢያቸው ተጽዕኖ ያደርግባቸዋል ።

*ፊጥራን* የሚቃወሙ ጠንካራ ሃይሎች ስላሉ አላህ ጥሩ ሰዎችን በየጊዜው እየመረጠ ትክክለኛውን ጎዳና በግልጽ ይነግራቸዋል። እነዚህ ሰዎች ነብያት ይባላሉ። በመሆኑም፣ ከአዳም ጀምሮ ያሉ ነብዮችን ስንመለከት የተላኩት የአላህን አንድነት ለማስተማር ነው ።

> ‹‹ ኢብራሂም ይሁዳዊም ክርስቲያንም
> አልነበረም ግን ወደ ቀጥተኛው
> ሐይማኖት የተዘነበለ ሙስሊም ነበር ።
> ከአጋሪዎቹ አልነበረም ። ››
>
> (ሱረቱል ኢምራን 3:67)

> ‹‹ (ቅጣትንም) ለነዚያ በስተፊትዋ
> ለነበሩትና ለነዚያም ከበኋላዋ ላሉት
> (ሕዝቦች) መቀጫ ለፈራህያን መገለጫ
> አደረግናት ››
>
> (ቅ:ቁ 2:66)

በአንድ አምላክ የማመን ጉዳይ አዲስ ወይም ያጋጣሚ ጉዳይ አይደለም- የቆየና መለኮታዊ ትዕዛዝ እንጂ። ኢስላም ይህን በተመለከተ መመሪያና አስተምህሮው ከዚህ ይመነጫል ። የሰው ልጅ በዚች ዓለም መኖር ከጀመረበት ዘመን ጀምሮ ፈጣሪያችን አላህ (ሱ.ወ) የሰው ልጆችን መሪና አስተማሪ አድርጎ የፈጠራቸውንና የመረጣቸውን በመካከላቸው በማስማራት እንዲያስተምሩ እንዲመሩና ምሳሌ እንዲሆኑ አድርጓል። ስለዚህ የተውሂደል ኢባዳ ዋና ክፍል ሽሪክን ማስፈፀሙ ነው ። ሺርክ ሰው የተፈጠረለትን ዋና ዓላማ የሚክድ እንደመሆኑ በአላህ ዘንድ እጅግ በጣም ከባድና ምህረት የማይደረግለት ኃጢአት ነው ። የሰው ልጅ ከሐጢአቱ እንዲድንና የአላህን ምህረት እንዲያገኝ ለዘላለማዊ ቤቱ መድህንና ለዓለማዊ ሕይወቱ ዘልዓለማዊ ፍፃሜ ወደደም ጠላም የአንድንና የብቸኛውን ፈጣሪ የሕይወት መመሪያ መከተል የግድ ይኖርበታል ።

## 2.3 ኢስላም ምንድን ነው? (ኢስላም ማለት ምን ማለት ነው ?)

ኢስላም ማለት ለፈጣሪ እጁን የሰጠ፣ በአላህ (ሱ.ወ) ሁለመናውን የጣለ፤ ፍፁም በሆነ መንገድ አላህን ያመነ ማለት ነው ። ፈጣሪ፣ጠባቂ፣የሁለንተናዊ ዓለም የበላይ ለሆነው አምላክ በትክክል አውቆና ተገንዝቦ ራሱን ያስገዛ

ብለን ተንተን አድርገን የጥሬ ቃሉን ትርጉም ማስቀመጥ እንችላለን ፡፡

ኢስላም በቃል የአላህ አንድነትና የነብዩ መሐመድን (ሰ.ዐ.ወ) መልክተኛነት (ላኢላሃ ኢልለላህ፣መሐመድ ረሱሉላህ) ብሎ ከመመስከር በልቦና ተቀብሎ በትክክል ከማመን ጋር የተያያዘ ሲሆን በአላህ ትዕዛዝና መመሪያ ከግለሰብ ጀምሮ ሁሉም ሙስሊም የቀን ተቀን ተግባሩ አድርጎ ሲያምንና ሲከተል ነው ፡፡ ሙስሊም ሊባል የሚችለው ማንኛውም ሁኔታ ሳያግደው ከዚህ አንፃር ሲፈፅም፤ የአላህን ፍላጎትና ትዕዛዝ ያለምንም ማወላወል ሲቀበልና ሲተገብር ነው፡፡ ኢስላምን ለመቀበል የሚፈልግ ሰው ማድረግ የሚኖርበት ከላይ የተጠቀሰውን የፈጣሪ አንድነት ማረጋገጥ ነው ፡፡ ይህ ምስክርነት ዛሬም በዓለም ላይ ሳለ በኋላም ከፈጣሪው ፊት ነፃ የሚወጣበት ነው ፡፡ የኢስላም ምንነትና ትክክለኛ መገለጫው ‹‹ ከአላህ በስተቀር ሌላ አምላክ የለም ›› የሚለው ሐረግ ነው፡፡ በአረበኛ አባባል ፡፡ ‹‹ ላኢላህ ኢልለላህ ›› የሚለው በአንድ በኩል አሉታን በሌላ በኩል ደግሞ አዎንታን የያዘ ሀረግ ነው፡፡አሉታዊ አንድምታው ‹‹ አምላክ የለም ሲሆን አዎንታዊው ደግሞ ‹ ከአላህ በስተቀር› የሚል የአላህን ‹አቻ የለሽነት› የሚያረጋግጥ ነው ፡፡ ታላቁ ፈጣሪያችን አምሳያ የሌለው ነው የሚለውን የሚያረጋግጥ ነው ፡፡

ለነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የተወረደው መለኮታዊ ሐይማኖት ኢስላም ይባላል ። ይህ መለኮታዊ መልዕክት በቅዱስ ቁርአን ላይ የተገለፀ ሲሆን በተመሳሳይ ሁኔታ ለሁሉም ነብያቶች የወረደላቸው ትዕዛዝ አንድና አንድ ነው ።

« አላህ ዘንድ (የተወደደ) ሃይማኖት፤
እስልምና ብቻ ነው እነዚያም መጽሐፍን
የተሰጡት ሰዎች በመካከላቸው ላለው
ምቀኛነት ዕውቀቱ ከመጣላቸው በኃላ
እንጂ አልተለያዩም በአላህም አንቀጾች
የሚክድ፤አላህ ምርመራው ፈጣን ነው ። »
(ቅ.ቁ 3፡19)

በኢስላም መርህ መሰረት ይህ ቀላል የሚመስል ቃል (ላኢላሃ ኢልለላህ) ኢማንንና (በአላህ ማመን) ኩፍርን (በአላህ መካድ) የሚለያይ ወሳኝ መሥመር ነው ። በዚህ የተውሂድ መርህ ምክንያት ኢስላማዊ እምነት አሃዳዊ ነው ። ኢስላም በዓለም ላይ ካሉ አሃዳዊ (ሞኖቴዝም) ሃይማኖቶች ከአይሁድና ክርስትና ጋር ይመደባል ።

ኢስላምን የተቀበሉ በቅዱስ ቁርአን « ሙእሚን » ይባላሉ ።

እያንዳዱ ሐይማኖት የራሱ የሆነ መርሆና መሰረታዊ መመሪያ አለው ። ኢስላም መሰረታዊ መርሆቹ እንደሚከተሉት ናቸው ።

ሀ. ላኢላሃ ኢልለላህ መሐመድ ረሱሉላህ። ይህም ማለት ከአላህ ሌላ አምላክ የለም መሐመድም መልዕክተኛ ናቸው ።

ለ. አምስት ወቅት ሶላት መስገድ (በቀን 5 ጊዜ በየተመደበለት ሰዓት መስገድ)

ሐ. በረመዳን ወር መጾም

መ. ምጽዋት (ዘካ) መስጠት ኢስላማዊ ግብር ይባላል ።

ሠ. ሀጅ-መንፈሳዊ ጉዞ ወደ መካ ማድረግ

ኢማን የሚለው ፅንሰ ሃሳብ በነብዩ ሐዲስ እንደተተነተነው (በጅብሪል (መላኩ ገብርኤል) አማካኝነት)

1. በአላህ ማመን
2. በነብዩች ማመን
3. በመለኮታዊ መጽሐፍት መውረድ ማመን
4. በመላዕክት (መላኢኮች) ማመን
5. በመጨረሻው ቀን ማመን
6. በቀደር ወይም በአላህ ውሳኔ ማመን

በቅዱስ ቁርአን ሱራ 2 አልበቀራ ቅድስና ወይም ሐይማኖተኝነት ሲገለፅ በማይታየው (ገይብ) እና በወህይ

(በተገለጡት) ላይ የጠና እምነት ያለው ነው ይላል። በመሆኑም አላህን በፀሎት እየተለማመነና ባለፀጋም ከሆነ ምጽዋት በመስጠት ሕይወቱን ሙሉ የሚገዛ ነው ።

በኢስላም ቅድስናና ሐይማኖተኝነት ማለት ሁሉንም ነብዩች አንዱን ከአንዱ ሳይለያዩ ማመን ሲሆን ነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ቅዱስ ቁርአን የተወረደላቸው ማጠቃለያው ነብይ መሆናቸውን በማረጋገጥ ለሌሎችም ነብዮች መለኮታዊ መጽሐፍ መመሪያ እንደነበራቸው ከዚህም በመነሳት የፈጣሪን ትዕዛዝ ያስተላልፉና ያስተምሩ እንደነበር ማረጋገጥ ከእያንዳንዱ ሙስሊም ይጠበቅበታል ።

## *2.4 አንድነት የሐሳብ ልዩነት በኢስላም*

የኢስላምን ታሪክ ስንመረምርና ስናጠና ኢስላማዊ አስተሳሰቦች እና መመሪያዎች እንዲሁም ኢስላማዊ ሥልጣኔ ይፋ እንደሚያደርጉት ኢስላምን በመከተልና የቀን ተቀን ሕይወትን በመምራት ረገድ የተለያዩ የሐይማኖቱ ት/ቤቶችና አስተምህሮት በጣም ብዙ በሆነ ዘዴና የማስተማር አቅጣጫ የሚገለጹ ቢሆንም ከመሰረታዊ ኢስላማዊ እምነት ውጭ ግን አይደሉም። በተለያዩ ኢስላማዊ ት/ቤቶች ልዩነቶች ቢኖሩም ሁሉም ከኢስላም መመሪያ (ከቅዱስ ቁርአን) እና ከነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ሱና እንዳልወጡ ያረጋግጣሉ ። የሚያጣቅሱት ሁሉ ከቁርአን

ወይም ከሐዲስ በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ ቢሆን እንጂ በልብ ወለድ የሚጽፉት ነገር እንደሌለ ያረጋግጣሉ ፡፡

በኢስላም ጥላ ስር ያሉ ሙስሊሞች ቁርአንን በመተርጎምና በመተንተን ረገድ እንደ ብቃታቸውና እንደ ግንዛቢያቸው ስፋትና ጥልቀት በመጠኑም ቢሆን የሚታዩ ልዩነቶች አሉ፡፡

በሙስሊሙ መካከል የማያከራክረው ነገር ግን ቁርአን መለኮታዊ መጽሐፍ መሆኑን በሁሉም ሙስሊም ዘንድ ልዩነት አለመኖሩ ነው ፡፡ በዚህ በኩል አንድነቱን የሚያናጋ አንዳችም ልዩነት የለም፡፡

ምንም እንኳን የተለያየ ፍልስፍና፣የሐይማኖት ጥናት የታሪክ ርዕሰ ጉዳዮች በሙስሊሙ መካከል የአስተሳሰብ ልዩነትና የአመለካከት ፍፁማዊ አንድነት ባይኖርም ነገር ግን ሁሉንም ሙስሊም የሚያስተሳስሩና የሚያጣምሩ (ኢስላማዊ ውጼታዎች ሱናዎች አሉ፡፡ እነሱም፡-

*ሀ.* በአላህ አንድነት ማመን (አልተወሂድ) ተውሃድ የሚለውን ቃል ለአላህ ስንጠቀም ወይም ‹ተውሂዱላህ› ስንል ከማንኛውም የሰው ልጅ ድርጊት ውስጥ የአላህን አንድነትና የበላይነት መቀበል ማለት ነው ፡፡ ድርጊት በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ ከአላህ ጋር ያገናኛል ፡፡

ለ. በነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ነብይነት ማመን በየቀኑ ሙስሊሙ ስግደት ሲፈጽም (ሲያከናውን) መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የአላህ መልዕክተኛ ናቸው የሚለውን በቃሉና በልቡ ያረጋግጣል ። ነብዩ መሀመድ (ሰ.ዐ.ወ) በ23 ዓመት የነብይነት ዘመናቸው ኢስላምን እስከ ህይወታቸው መጨረሻ ድረስ በሚገባ ያስተማሩ ታላቅ ነብይ ነበሩ ።

ሐ. በነብዮች ሁሉ ማመን፡- ዓለም ከተፈጠረች የሰው ልጅ በዚህች ዓለም ከመጣ ጊዜ ጀምሮ በአላህ (ሱ.ወ) የተላኩ ነብዮችን በሙሉ ሁሉም ሙስሊም አምኖ ይቀበላል ። በተላኩበት መንገድ ለሰው ልጆች መልዕክቱን ለማደረስ ፍትህ፣ ነፃነትና፣ የአላህን አሃዳዊነት፤ ለማስፈንና ለማስተማር ያደረጉትን ያላሰለሰ ጥረት ሁሉ ሙስሊም የሆነ ሁሉ ያምናል ።

መ. ቁርአን መለኮታዊ መጽሐፍ ስለመሆኑ ማመን። ቁርአን መለኮታዊ ቃል ነው። ይህንንም ሙስሊም የሆነ ሁሉ በእውነት አምኖ ይቀበላል ። የሐይማኖቱ ሊቃውንት የቁርአንን ትርጉም በተመለከተ የሐሳብ ልዩነት የሚያሳዩባቸው ቢኖሩም የሚስማሙባቸው ያመዝናሉ ።

ሠ. ከሞት በኋላ ሕይወት፡- (ዘለዓለማዊ ሕይወትን) በተመለከተ ሁሉም ሙስሊም ያለምንም ዓይነት ልዩነት ከሞት በኋላ ስለሚኖረው ሕይወት ይስማማል ። በቅዱስ ቁርአን እንደተጠቀሰው በዚች ጊዜያዊ ዓለም የአላህን ትዕዛዝ ያከበረና በመልካም ምግባሩ የፀና ሰው ሁሉ የአላህን (ሱ.ወ) ምርቃትና ሽልማት እንደሚያገኝ ሁሉ የተሳሳተውን መንገድ የተከተለ ሃጢአተኛ ደግሞ ምንዳው ቅጣት እንደሚሆን በርግጠኝነት ያምናሉ ። ትንሳኤ ስለመኖሩ በአላህ (ሱ.ወ) ፊት ለፍርድ መቅረብን በማያወላዳ ሁኔታ ይቀበላሉ ።

ረ. ተዘወትሮ የሚከናወን ሐይማኖታዊ ሥርዓት፡- ሙስሊሞች አዘወትረውና በዕድሜያቸው አንድ ጊዜ የሚፈጽሟቸው ሐይማኖታዊ ሥርዓቶት አሉ ። እነዚህም በየቀኑ አምስት ጊዜ መስገድ (አምስት ወቅት ሶላት) ፣ በየዓመቱ የረመዳንን ወር መጾም ፣ በሕይወታቸው አንድ ጊዜ ግዴታ የሆነውን ሐጅ ማድረግ (ለቻለ ገንዘቡ ላለው) የመሳሰሉትን በጣም ቀላል በሆኑ ሁኔታዎች የሚለያዩባቸው ቢኖሩም በአጠቃላይ ግን የሙስሊሙ የጋራ ተግባራት ናቸው ።

እስልምና በቅዱስ መጽሐፋችን በቁርአንና በታላቁ ነብይ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) አማካይነት ከተስፋፋ ወዲህ በአማኞች መካከል በኢስላማዊ አስተምህሮትና በፍልስፍናው ረገድ በሚፈጠሩ አለመግባባቶች የተከሰቱባቸው ወቅቶች ነበሩ። ያም ሆኖ ግን በኢስላም መተክል ላይ ሁሉም ፅኑ አቋም ነበራቸው (አላቸው) ።

## 2.5 ሺአና ሱንኒ

ሙስሊሞች ሺአ እና ሱንኒ በተባሉ ሁለት ቡድኖች የተከፈሉ ናቸው ። አንዳንድ ፀሐፊዎች ሐሪጅዎችን (አፈንጋጮችን) እንደ ሦስተኛ ቡድን ይቆጥሯቸዋል ። ነገር ግን ይህ የአመዳደብ ስልት ትክክል አይደለም ። ሐሪጂዎች (ሁዋሪጅ) በአንድ የታሪክ አጋጣሚ የተፈጠሩ ሲሆኑ አሁንም በጣም ጥቂቶች ብቻ አሉ ። በመሆኑም እነርሱን በዚህ አላካተትናቸውም ።

ሱንኒዎች ከሙስሊሙ ሕዝብ ከፍተኛውን ቁጥር የያዙ ሲሆን 87%- 88% ይሆናሉ ። የነብዩን ሱንና በትክክል የምንከተል እኛ ነን ይላሉ ። ሺአዎች ከጠቅላላው ሙስሊም 12%-13% ያህል ናቸው ። ከነብዩ ሞት በኋላ በተፈጠረው መከፋፈል የተፈጠረው ሺአ በአሊ (ዐ.ሰ) እና በልጆቻቸው ላይ

ከፍተኛ እምነት አላቸው። ሺአዎች በኢማሞች የተከፋፈሉ ናቸው ። 12ቱ ኢማሞች ብለው በሚጠሯቸው እጅግ በጣም የጠነከረ እምነት አላቸው። ዛይዲዎች የሚባሉት የኢማም ዛይድ ተከታዮች ሲሁኑ፣ (የአራተኛው ኢማም ልጅ) ኢስማይሊዎች የሚባሉት ደግሞ የኢስማኢል ተከታዪች (ከኢማም ሳዲቅ ልጆች አንዱ) ናቸው ። እነዚህ ኢማሞች (ሺአዎች) በሙስሊሙ ጠቅላላ ብዛት 130 ሚሊዩኑን ያህል ይይዛሉ ። የሚኖሩትም በኢራን፣ኢራቅ፣ሊባኖስ እና በፋሪስ ባህረሰላጤ ባሉት አገሮች በአፍጋንስታን፣አዘርበጃን፣ፓኪስታንና ሕንድ ውስጥ ነው ።

በሺአና በሱኒዎች መካከል የተፈጠረው ልዩነት ምክንያቶች ከነብዩ መሀመድ (ሰ.0.ወ) ሞት በኂላ ተተኪ ከሊፋዎች በመምረጥ ረገድ ሺአዎች ስህተት ተፈፅሟል ብለው በፈጠሩት ልዩነት ነው ። ሱኒዎች አቡበከር በሕዝቡ (በሕዝበ ሙስሊሙ) ጽምፅ የመጀመሪያው ከሊፋ ሆኖአል ሲሉ ሺአዎች በበኩላቸው ይህ የከሊፋነት ሥልጣን አሰጣጥ ፓለቲካዊ ይዘት ብቻ ሊኖረው አይገባም ከሌሎች ሁኔታዎች አንፃርም መገምገም ይኖርበታል ። የሚል አቋም ያዙ ። ይህንም ሲሉ ከሊፋ የተመራጩ

የሐይማኖት እውቀት ስለ ፍትህ ያለው ጠንካራ አቋም በአጠቃላይም ቅዱስ ቁርአንን የመተርጎምና ኢስላምን በትክክል በመተርጎም በኩል አንቱ የተባለ መሆን ይገባዋል ይላሉ ።

ሺአዎች እንደ ሱንኒ ሁሉ ነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የመደምደሚያው ነብይ መሆናቸውን ያምናሉ ።

ከነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) በኋላ ሌላ ነብይ እንደማይመጣም በቅዱስ ቁርአን በተገለፀው መሰረት በትክክል ያምናሉ ። ነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) መሰል እውነተኛ የአላህ መልዕክተኛ የሚተካ ባይገኝም ኢስላማዊ አስተምህሮቱ ግን ከፋም በጀም ቀጣይ ሆኖ ይገኛል በማለት አስተያየታቸውን ይገልፃሉ ። በመንፈሳዊ ደረጃቸው የላቁ ኢማሞች ኢስላምን ጠብቀው በማቆየት ረገድ ከአላህ (ሱ.ወ) ሃላፊነት ተጥሎባቸዋል ። ከሊፋዎችን በመተካት መልካም ሥነምግባርና ተግባር ለተከታዮቻቸው በማሳየት ሃላፊነታቸውን ይወጣሉ በማለት የሺአ ሙስሊሞችን ያስተምራሉ ። የኡመያድ ሥርዎ መንግስት የታሪክን አቅጣጫ በማስቀየር ኢማሜት (የሺአ መሪዎች) በከሊፋዎች እንደተተካና ሥር መሰረቱን ለቆ እንደነበር ያስረዳሉ ።

የሺአ የእምነት መመሪያ ይፋ የመንግስት መመሪያ የሆነው በሳፋቪድ ዘመነ መንግስት በ1501 A .D (በ922 ዓ.ሂ) ነበር ፡፡ በ1979 የሺአ መንግስት ሲመሰረት የመሰረቱት የኢስላማዊ አብዮት መሪ አያቶላህ ኾሜይኒ ነበሩ ፡፡ እኒህ ሰው ኢስላማዊ ሪፐብሊክ ኢራንን በመመስረት የኢስላም አስተምህሮት በሁሉም ሁኔታና ጊዜ ተግባራዊ እንዲሆንና የሺአ አስተሳሰብም ከዚህ አንፃር የእምነቱን ቀኖናና ፓለቲካዊ አካሄዱን እንዲመራ አድርጎታል ፡፡ ማህበራዊና ኢኮኖሚያዊ ጉዳዮች ከሕዝቡ ጥቅምና ብልጽግና አንፃር ተቃኝተው በትምህርቱ ዘርፍ የላቀ ሚና እንዲጫወቱ መሰረት ጥለዋል ፡፡ የኢስላማዊ ሪፐብሊክ ኢራን መንግስትም የሺአን የሐይማኖት መመሪያ በዘመናዊው ዓለም ለሚገጥሙ ችግሮች መፍቻ መንገድ ነው ብለው በእግጠኝነት ያምናሉ ፡፡

## 2.6 ኢስላም እንደ ሐይማኖት

ቅዱስ ቁርአን እንደሚያስቀምጠው ከአላህ ዘንድ የተወደደው ሃይማኖት እስልምና ብቻ ነው ፡፡ይላል ፡፡

‹‹ አላህ ዘንድ (የተወደደ) ሃይማኖት

እስላምና ብቻ ነው ፤እነዚያም

መጽሐፍን የተሰጡት ሰዎች በመካከላቸው

ላለው ምቀኝነት ዕውቀቱ ከመጣላቸው

በኂላ እንጂ አልተለያዩም ።

በአላህ አንቀጾች፣የሚክዱ አላህ

ምርመራው ፈጣን ነው ። ›› (ቅ.ቁ 3፡19)

ቀደምት ነብዮችን በተመለከተም አላህ (ሱ፣ወ) እንዲህ ይላል

‹‹ ኢብራሂም ይሁዳዊም ክርስቲያንም

አልነበረም ግን ወደ ቀጥተኛው

ሃይማኖት የተዘነበለ ሙስሊም ነበረ።

ከአጋሪዎችም አልነበረም ። ››

(ሱረቱ አሊ-ኢምራን 3፡67)

የሐይማኖት ቃል መሰረተ-አመጣጡ ማለት ‹ አል-ዲን › የሚለው ሰፊ ትርጉም ካለው አል - ዲይን ማለት አደራ ወይም ውለታ ያለበት የሚል አንድምታ አለው ። ይህም ሲሳይ ለጋሽ ፤ማናቸውንም ነገር አንቀሳቃሽ፣ ሕያው አድራጊ፣ ሕይወት ነሺ ለሆነው በጣም ሩህሩህ በጣም አዛኝ ለሆነው ፈጣሪ አላህ (ሱ.ወ) የሰው ልጅ ያለበትን አደራና እንዲሁም ውለታ የሚያመለክት ቃል ነው ። ይህን እዳ ለመክፈል የሰው ልጅ ሕይወቱን ሙሉ ቢጥርም ሊከፍለው የሚቻለው አይሆንም ሁለንተናዊ ዓለምን እና ሰዎችን የፈጣሪ አላህ (ሱ.ወ) ለዚህ ቸርነቱና ልግሥናው የሚከፈለው ነገር ቢኖር

‹አልሃምድሊላህ› (ምሥጋና) ብቻ ነው ። የሰው ልጅ ፈጣሪውን ሲያስታውስ የቁርአንን አንቀጽ ሊያስተነትን ይገባዋል ። ከሱረቱል ዩኑስ 10፡31 እንደ ምሳሌ እንውሰድ ።

‹‹ ከሰማይና ከምድር ሲሳይን
የሚሰጣችሁ ማን ነው ? መስሚያዎችን
ማያዎችንስ የፈጠረ ማን ነው ?
ከሙትም ሕያውን የሚያወጣ ፣
ከሕያውም ሙትን የሚያወጣ ማን ነው ?
ነገሩን ሁሉ የሚያስተናብርስ ማን
ነው? በላቸው። በእርግጥም አላህ ነው ፡ይሉሃል ።
ታዲያ (ለምን ታጋራላችሁ)
አትፈሩትምን ? በላቸው ። ››

እስከአሁን ከተጠቀሱት የቁርአን አንቀጾች እንደምንረዳው ከሐዲዎች የአላህን ልዕልና፣ኃይልና ሥልጣን እንደሚያውቁ ነው ። በርግጥም በሙሉ እምነት ያመልኩትም ነበር ። አላህ የተብቃቃ ጠቃሚና ሁሉን አድራጊ ጌታ ነው ። ቁርአን ይህን ሐቅ በተመለከተ በግልጽ አስቀምጦታል ።

‹‹ እናንተ ሰዎች ሆይ! እናንተ (ሁል ጊዜ)
ወደ አላህ ከጃዮች ናችሁ
አላህም እርሱ ተብቃቂው ምስጉን ነው ። ››

(ቅ፣ቁ 35፡15)

የአላህን ዕውቀት ስፋት፣ጥልቀትና ሁለገብነት የሚያመለክቱ ቁርአናዊ አንቀጾች በርካታ በመሆናቸው ሁሉንም መጥቀስ አዳጋች ነው ። በሰማይም ሆነ በምድር አንድም ነገር ከርሱ ድብቅ አይደለም ። ትንሽም ነገር ሆነ ትልቅ ከርሱ ‹‹ዒልም›› የሚያመልጥ የለም ። አላህ የሚዘነጋውም ሆነ የሚረሳው ነገር የለም ። የሰው ልጅ ምንም ያህል ጥልቅ እውቀት ቢኖረው ከመለኮታዊ ዕውቀት ጋር ሲነፃፀር ኢምንት ነው ። የአላህ ዕውቀት በየትኛውም የዓለም ክፍልና ዩኒቨርስ የሚደርስ ነው ። አላህ ወሰን በሌለው መጻኢ ጊዜ (ሙስተቅበል) የሚከሰተውን ነገር ሁሉ ያውቃል ። የአላህ ዒልም ግልጽና ምስጢር የሆኑ ነገሮችን ሁሉ የሚዳስስ ነው ። ምንም ነገር ከርሱ የሚደበቅ አይኖርም ። በመሆኑም እኛ ፍጡራን ሐይማኖት እንዲኖረን የሐይማኖት ትዕዛዛትንም እንደናከብርና እንድንፈጽም ካልቻልን ሕይወታችን ሁሉ ከንቱ ይሆናል ። ቀኑ ይጨልምብናል ፡የምንጨብጠውና የምንይዘው ሁሉ ይጠፋብናል ። እምነት የሌለው ሰው ለብርቱ ቅጣትና ተግሳጽ ያበቃዋል ።

ሐይማኖት ፓለቲካ፣ሥነ ጥበብ፣ ማህበራዊ ውይይት ወይም ፍልስፍና አይደለም ። ነገር ግን ሐይማኖት (እምነት) በሰው ልጅ መላ ሕልውና ውስጥ ያለ መንፈስ ነው ። ሐይማኖት

የአንድን ሰው ሕይወት ትርጉም ያለው የሚያደርግ በተስፋ በሰላም እና በደስታ፣የሚያኖር ነው ይህን በተመለከተ ቅዱስ ቁርአን እንዲህ ይላል ፡-

‹‹ እናንተ ያመናችሁ ሆይ!
(መልክተኛው)ሕያው ወደሚያደርጋችሁ
እምነት በጠራችሁ ጊዜ ለአላህና
ለመልዕክተኛው ታዘዙ አላህም
በሰውየውና በልቡ መካከል የሚጋረድ
መሆኑን ወደርሱም የምትሰበሰቡ
መኾናችሁን ዕወቁ ። ››

(ቅ.ቁ 8፡24)

እምነት (ሐይማኖት) የአንዱን አማኝ የውስጥ የውጭ፣የግል እና ማህበራዊ ባህሪን የሚወስን በመጨረሻም አይቀሬውን ሞት እንደሚቀምስ የሚያረጋግጥ ነው ።

## 2.7 ቀጥታ ግንኙነት

አላህ (ሱ.ወ) ለሰው ልጆች ከደም ሥሮቻቸው በጣም የቀረበ ነው ። በመሆኑም ተማጽኖና ልመናው ሁሉ በቀጥታ ለፈጠረው ጌታ መሆን ይኖርበታል ። ቢጣራ የሚሰማው፣ቢቸገር የሚያየው፣ቢጨነቅ የሚያዝንለት

በአጠቃላይ ለዱአው (ለፀሎቱ) ምላሽ የሚሰጥ ሁሉን አዋቂ ጌታ ብቻ መሆኑን አውቆ ወደ እርሱ ሊጠጋ ይገባዋል ።

የሐይማኖት ቅድመ ሁኔታና ዋና ዓላማ የሰው ልጅ ከፈጣሪው ጋር ቀጥተኛ የሆነ ግንኙነት ለመፍጠር እንዲችል ማስተማር ነው ። አንድ ሰው ከእርሱ (ከአላህ) እንዲጠይቁለት በማሰብ ጸሎቱን ለቅዱሳን ተብዩዎች ለጂኖች ወይም ለመላእክት ማድረግ አይኖርበትም።

የመድህን ዋና ምንጭ አላህ ብቻ ነው ። ስለዚህ የአንድ ሰው የነፍስ ወከፍ እምነት ወይም እስልምና የሚረጋገጠው ከአላህ ጋር በሚፈጥረው ቀጥተኛ ግንኙነት ነው ።

## 2.8 የኢስላም ማህበራዊ ሁኔታ /ሞገስ/ገጽታዎች

እንደ እንከን የለሽና ሚዛናዊ ሃይማኖት እስልምና የሰው ልጆችን የሕይወት ገጽታዎች ከፖለቲካ፣ ማህበራዊና ኢኮኖሚያዊ እሴቶች አንጻር ይመረምራል /ይገነዘባል። ከዚህ እጅግ ተቃራኒ በሆነ ሁኔታ ሌሎች አንዳንድ ሃይማኖቶችና ተቋማት እንደሚከራከሩት ፤ሃይማኖት እንዲያውም በጭራሽ የሰው ልጆችን ህይወት ወይም የኑሮ ዘይቤ በጣም ጠለቅ ባለ ሁኔታም ሆነ፣ሚስጥራዊ የሕይወት ገጽታዎችን አይመረምርም ወይም አይገነዘብም ብለው ያምናሉ ።

እንደ አንዳንዶች አመለካከት እስልምናን ሰናየው፤ እስልምና መጠነ ሰፊና፣በቀላሉ የማይለካ፣ ረቂቅ በሆነ

መንገድ ከአምላክ ጋር የሚገናኙበት ብቸኛው መንገድ /ሐይማኖት/ እንደሆነ ለማስተዋወቅ ይህ ነው የማይባል ጥረት አድርገዋል ። ነገር ግን ይህ ዓይነት አቀራረብ በቅዱስ ቁርአንም ሆነ በነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) እና የሰሃባዎች የመሃበራዊ ኑሮ አስተምህሮት ጋር ሲነጻጸር በጭራሽ ተቀባይነት የለውም ።

እንደ ኢስላም በዚህች ዓለም እና በወዲያኛይቱ ዓለም ወይም በቁስአዊዋ እና በቅዱሷ ዓለም፤ እምነት፣ልምድ ወይም ምግባር እና ብልጽግና ለብቻቸው ተነጣጥለው የሚታዩ ሳይሆን ይልቁንም የተያያዙ ና የጋራ በሆነ መልኩ የሚታዩ ናቸው።

ኢስላም ህብረተሰብን በተመለከተ ሲያስተምር የሕብረተሰብ ሕይወት ብሎ የሚጠቅሳቸው ቤተሰብን ሙስሊሙን ህብረተሰብ (ሙስሊም ዑማህ) በሙስሊሙ ህብረተሰብ መካከል ያለውን ግንኙነት እና ሙስሊሙ ህብረተሰብ ከመንግስት ጋር ያለውን መስተጋብር፤ ከሰዎች ጋር ያለን ግንኙነት፣ ከእንሰሳት፣ ከአካባቢ ጋር ያለውን ሁለንተናዊ ግንኙነትና መስተጋብር ነው ። በዓለም ላይ ያለው ግዑዝና ሕይወት ያለው ፍጥረት ሁሉ በሰው ልጅ ላይ የራሱ ተጽዕኖ አለው ።የሰው ልጆች ብልጽግና እና ዕድገት ተፈጥሮአዊ ክስተት በሚኖራቸው ሚና መሰረት

የዕለት ተዕለት ሁኔታዎችና እንቅስቃሴዎች በዕቅድ የሚመሩበትን መንገድ ኢስላም ያመቻቻል ።

በህብረተሰብ አባላት መካከል የሚኖርን ግንኙነት ኢስላም ጠቃሚ ቦታ ይሰጠዋል። በወላጆች መካከል፣ በእህትና ወንድም ፣እናትና አባት በልጆቻቸው መካከል ጎረቤት ከጎረቤት ጋር ፣መምህር ከተማሪዎች ጋር ሙስሊም ከሙስሊም ወንድሙ ጋር ሙስሊም ከሌላው አማኝ ጋር የሚያደርገውን ግንኙነት ኢስላም ከፍተኛ ትኩረት ይሰጠዋል ። ሙስሊሙ ህብረተሰብ የሚተዳደርባቸው ሞራላዊ እሴቶች፣ህግና ደንቦች ያሉት ሲሆን መብትና ግዴታ፣ ተጠያቂነትና ኃላፊነትን በግልጽ ያስቀመጠ አሰራር በኢስላም በአግባቡ ተደንግጓል ። በቁርአንና በነብዩ ሐዲስ በግልፅ የተቀመጡት መመሪያዎችና ደንቦች ሙስሊም ያልሆነ የህብረተሰቡ አካል ኢስላማዊ አመራርና ሸሪአን በምታስተናግድ አገር በምን ሁኔታ መብትና እምነታቸው ተጠብቆ መኖር እንደሚችሉ ደንግጓል ። ኢስላም ሙስሊም ያልሆኑ የህብረተሰብ አባላትን በግዳጅ ወደ እምነቱ የሚያመጣ ሐይማኖት እንዳልሆነ አረጋግጧል ።

## 2.9 ኢኮኖሚያዊ ትምህርት

የአንድ ሕብተሰብ የህልውና መሰረት ተብለው ከሚጠቀሱት ጉዳዮች ውስጥ አንዱ ምጣኔ ሀብታዊ እውቀትና አመራር ነው ። እንደ አንዳንድ አስረተምህሮ

ምጣኔ ሀብት የባሕል የአስተሳሰብ ሞራላዊ እሴት መሰረት ተደርጎ በኢስላም አይወሰድም ። ነገር ግን የተበላሸ ኢኮኖሚያዊ ወይም ምጣኒያዊ ሀብት የሚፈጥረው ግንኙነት የአንድን ህብረተሰብ ማህበራዊ፣ሞራላዊ እና ባህላዊ ዝቅተትን ሊያስከትል ይችላል ። በቅዱስ ቁርአን ይህን በተመለከተ ብዙ የቁርአን አንቀጾችን ለድህነት፣ለውርደት እና በማህበረሰቡ ውስጥ የመደብ መከፋፈል መፈጠር ምክኒያት የሃብት አጠቃቀም አለመስተካከል መሆኑን ያረጋግጣል ። ድህነት ለእምነት ሚዛን መዛባት፣መሰረታዊ የእምነት መርሆዎች መጣስ አደገኛ የህብረተሰብ ክፍል መፈጠርን የሚያመቻች ሁኔታ ነው ። በመሆኑም ኢስላም ፍትሃዊ የምጣኔ ሀብት ሥርዓት የመኖርን አስፈላጊነት በብርቱ ያስተምራል ። መሰረታዊ የሆኑ የሰው ልጅ ፍላጎቶች (ምግብ፣መጠለያ አልባሳትና በትዳር ውስጥ መኖር ወይም ጋብቻ ) በተቻለ መጠን ሊሟሉ ይገባል ። አንድ የህብረተሰብ አባል መንፈሳዊ ተግባሩንና ሌሎች በሁለተኛ ደረጃ የሚያስፈልጉትን ነገሮች ለመፈፀም መሰረታዊ ፍላጎቶቹ ሊሟሉለት ይገባል ። እንዲህ መሆን ካልቻለ ለአንድ ችግረኛ ድሃ ስለ ፈጣሪው፣ስለ ሐይማኖት፣ስለ መንፈሳዊነት ፍቅርና ነፃነት ለማስተማር በፍፁም አይቻልም።

ኢስላማዊ ምጣኔ ሀብትን በተመለከተ ብዙ ትምህርቶች ያሉ ሲሆን የንግድ ሥርዓት፣ገንዘብ መሰብሰብና ማከፋፋልን፣ታክስ አከፋፈል ፣ወቅፍ (ኢንደውመንት) ስለ ድህነት፣ ወለድ፣ የሀብት ባለቤትነት እና የመሳሰሉትን በምን ዓይነት ሁኔታ መያዝና ጥቅም ላይ መዋል እንዳለባቸው ግልጽ ድንጋጌዎች አሉ ።

እነዚህ ድንጋጌዎች ከሽሪአው አንፃር በግድ ተፈፃሚ የሆኑና ወይም ደግሞ ከሞራላዊ እሴት አንፃርና ከኤኮኖሚያዊ መመሪያ አኳያ የሚታዩ ናቸው ። በዚህ መልክ ለዘመናት ሙስሊሙ ህብረተሰብ በመርህነት ሲጠቀምባቸው የቆዩ ከሽሪአው ያልወጡ አሰራሮችም ጭምር ታሳቢ ይሆናሉ ።

የኢስላማዊ አስተምህሮት አካል ከሆኑት ውስጥ ፓለቲካዊና ወታደራዊ ደረጃዎች በሙስሊም ህብረተሰብ ትልቅ ቦታ አላቸው። ወታደራዊ ተቋሞች የሚገነቡትና የሚጠናከሩት አገርንና ድንበርን ለመከላከል ሲሆን ከዚህ የዘለለ ዓላማ የላቸውም ። ብዙ ሙስሊም ምሁራን እንደሚስማሙበት ጀሃድ ወይም አንዳንዶቹ ቅዱስ ጦርነት ብለው የሚጠሩት የሚታወጀው ከመከላከል አኳያ እንጂ በእብሪት የሌላን አገርና ድንበር ለመድፈር አይደለም ። ቅዱስ ቁርአንና የነብዩ የዕለት ተዕለት ተሞክሮዎች እንደሚያስረዱን ጅሃድ ቀዳማዊ ትርጉሙ ራስን (ነፍስን)

መቆጣጠር ሲሆን፣ገፍቶ ለመጣ ወራሪ ደግሞ ከመከላከል አንፃር የሚደረግ ጦርነት ነው ። ሌላው ኢስላም የሚያስተምረን ነገር በጦርነት ወቅት ከጠላት ወገን የሚማረኩትን የጦር እስረኞች በአግባቡ መያዝና በጦርነትም ወቅት ሲቪሉን ሕዝብ ላለመጉዳት ከፍተኛ ጥንቃቄ ማድረግን ነው ።

## 2.10 <u>*የፓለቲካ መብቶች*</u>

የፓለቲካ መብቶችን በሚመለከት ኢስላም ግልጽና ልዩ የሆነ የሕዝብ ሃላፊነትን ደንግጓል ። በምን ሁኔታ ኢስላማዊ መንግስት መመስረት እንደሚቻል፣ ፍትህና ነፃነት ያለበት የተደለደለ ሥርዓት መመሥረትን በተመለከተ በዝርዝር ተንትኗል ። በተዋቀረው መንግስት በሐይማኖቶች መካከል መቻቻልን፣ ፍትሃዊ አስተዳደርን፣ ትምህርትን በሚመለከት ሊኖራቸው የሚገባውን ቦታ ይደነግጋል ። በአጭሩ መንግስት ለህዝቡ ማድረግ ያለበትንና በአንፃሩም ህዝብ ለመንግስት ማድረግ ያለበትን መብትና ግዴታዎች ይተነትናል ። መንግስትና ፓለቲካን በሚመለከቱ ጉዳዮች የተጠቀሱት የሚከተሉት ናቸው ።

*ሀ.* መንግስት ከኢስላማዊ አመለካከት አንፃር ስናየው ቀዳሚ ተግባሩ የሚመራውን ህብረተሰብ ወደ

ፈጣሪው የሚቃረብበትን ሁኔታ ሁሉ ማመቻቸት ነው። ይህም ሆኖ ግን መንግስት የሕዝቡን ብልጽግናና ፍትህ ነፃነት፣ደህንነት እና መሰል ሁኔታዎችን መፍጠር ይጠበቅበታል ።

ለ. በመንግስት ቅርጽና አደረጃጀት ዙሪያ ላይ ያተኮረ መንግስት ሳይሆን በህዝቦችና መንግስት ግንኙነት ላይ ትኩረት የሠጠ፣በመሪዎችና በተመሪዎች መካከል ፍትሃዊ መስተጋብር እንዲኖር የሚጥርና ሐላፊነቱን የሚወጣ መንግስት ሊሆን ይገባዋል ።

ሐ. ሐይማኖትን የሚከተል መንግስት ለመለኮታዊ ትዕዛዝ ታማኝ የሆነ ለመመሪያና ደንቦች ተገዥ የሆነ መሆን ይኖርበታል ። ለተከበሩ የእምነቱ ዓላማዎችና እሴቶች ተግባር ላይ መዋል ያለሰለሰ ጥረት የሚያደርግ ሆኖ ከተጨባጭ ሁኔታ አንፃር ሐይማኖቱን የማይፃረሩ ሳይንሳዊ ምርምርና ጥናቶችን በማካሄድ የሕብረሰተሰቡን ልምድ ወደ ላቀ ደረጃ ማድረስ የሚችል እውነተኛ መንግስት መሆን አለበት ።

መ. በኢስላማዊ ባህል ሐላፊነትና መብት የተያያዙ ናቸው ። በመሆኑም መሪዎቻቸውን በመምረጥ፣ በመውቀስ እና በመቃወም ረገድ ሙሉ መብት ያላቸው ሲሆን፤ከመረጧቸውም ከላይ እስከ ታች

ለሚገኙት መሪዎች በሥርዓት መታዘዝና ማገልገል የግድ ነው ።

ሠ . ኢስላም ግለሰብ ባሰበውና በተመኘው መንገድ በመጓዝ በነፃነትና በልበ ሙሉነት ሊበለጽግና ሊያድግ ይችላል ይላል ። በመሆኑም ኢስላማዊ መንግስት እምነቱን እንዲያጠናክር በነፃነት እንዲያስብ እንዲመራመር መንገዱን ሊጠርግ መቻል ይኖርበታል። ስለዚህ ኢስላማዊ ህብረተሰብ የተለያየ የፖለቲካ፣የኢኮኖሚ፣የፍልስፍናና ብሎም የእምነት አስተሳሰብ መኖር እንዳለበት ያምናል። ይቀበላል ። እንደዚሁ መሰሉ የተለያዩ አመለካከትና ግልጽ ውይይቶች ሙስሊሙን ህብረተሰብ ያሳድገዋል ብሎ ያምናል ።

# ምዕራፍ 3

# ኢስላማዊ መርህዎችና እምነቶች

## 3.1 ፈጣሪ

ተውሂድ የኢስላም መሰረት መሆኑን በትክክል የሚገለፀውም ‹‹ ላኢላሀ ኢልለላሀ›› (ከአላህ በስተቀር ሌላ አምላክ የለም) በሚለው ሀረግ መሆኑ በሁሉም ዘንድ የሚታወቅ ነው ፡፧ ይህም ቃል የሚገልፀው አንድ ብቸኛ እውነተኛ ጌታ መኖሩንና አምልኮም ተገቢ የሚሆነው ለእርሱ ብቻ መሆኑን ነው ፡፧ የአላህ ስሞች ተውቂፊያ ናቸው፡፡ ይኸውም የሰው ልጅ ሕሊና (ዐቅል) ስለነዚህ ስሞች በቁርአንና በሐዲስ ከተነገረውና ከተገለፀው ውጭ ትርጓሜ ሊሰጥ ከቁርአንና ከሐዲስ ቀጥተኛ መልዕክት በተለየ መለኮታዊ ሂስ ሊሰጥባቸው አይፈቀድለትም ፡፡ ምክኒያቱም የሰው ልጅ አእምሮ ስለ ፈጣሪው ስሞችና ባሕሪያት ውስጣዊ ይዘት በጥልቀት የማወቅ ችሎታና ብቃት የሌለው

በመሆኑ ነው ። ቅዱስ ቁርአን በምዕራፍ 37 አንቀጽ 180 እንዲህ ይላል፡፡

« የማሸነፍ ጌታ የሆነው
ጌታህ ከሚሉት ሁሉ ጠራ »
(ቅ.ቁ 36፡180)

« ሰማይና ምድርን ፈጣሪ ነው ።
ከነፍሶቻችሁ (ከጎሶቻችሁ) ሴቶችን፣
ከቤት እንሰሳዎችም ዓይነት
(ወንዶችና ሴቶችን) ለናንተ
አደረገላችሁ በርሱ (በማድረጉ) ያበዛችኋል ።
የሚመስለው ምንም የለም እርሱም
ሰሚው ተመልካቹ ነው ። »

(ቅ.ቁ 42፡11)

ለሰው ልጅ ከደም ጋኑ (ሥሩ) ጅማት ይበልጥ ወደ እሱ ቅርብ ነኝ ሲል አላህ በቁርአኑ ይገልፃል ። በየትኛውም አቅጣጫ ብትዞር በአላህ ቁጥጥር ሥር ነህ የሚባለው የአዋቂዎች አባባል ይህን ያጠናክረዋል ።

‹‹ ምስራቁም ምዕራቡም የአላህ ነው ፡፡
(ፊታችሁን) ወደ የትም ብታዞሩ
የአላህ ፊት እዚያ ነው ፡፡ አላህ
ችሮታው ሰፊ አዋቂ ነውና ››

(ቅ.ቁ 42፡11)

የቁስአካል አራማጅ ኦሬንታሊስቶች አላህ (ሱ.ወ) ራሱን የጠራበትን ስሞች አይቀበሉም፤ ሌላ ስያሜ በመስጠት የአላህን መብት (ሐቅ) ይዳፈራሉ ፡፡ ኢስላም ፈጣሪን (አላህን) "አልፋናአሚጋ" ይለዋል የመጀመሪያም መጨረሻም የሌለው ነዋሪ ነው ይላል ፡፡

‹‹ እርሱ ፊትም ያለ ኋላም ቀሪ
ግልጽም ስውርም ነው ፡፡ እርሱም
ነገሩን ሁሉ አዋቂ ነው ፡፡ ››

(ቅ.ቁ 57፡3)

ሁሉም ወደ እርሱ ተመላሽ (ሚች) መሆኑን ማመን የአንድ አማኝ ግዴታ ነው ፡፡ ቁርአንም በምዕራፍ 2 አንቀጽ 156 ላይ በግልፅ አስቀምጦታል ፡፡

‹‹ እነዚያን መከራ በነካቸው
ጊዜ እኛ ለአላህ ነን እኛም ወደ

እርሱ ተመላሾች ነን የሚሉትን (አብስር) ››

አላህ ፍጡራንን በሚበጅ መልኩ ዓለምን የፈጠረ ሲሆን ትክክለኛውን መንገድ ለተከተሉ ሁሉ ግልጽ አመራሩን በመስጠት የሕይወታቸው ብርሃን የኑሮአቸው አለኝታ በመሆን የሚኖሩባትን አለም በሥርዓት እንዲጠቀሙባት ያደርጋል ።

ይህችን ሁለንተናዊ ዓለም የሰው ልጆችና ሌሎች ፍጡራን እንዲኖሩባት አድርጎ የፈጠረ ብቻ ሳይሆን እንዲጠቀሙባትም ጭምር ሁሉን ነገር አመቻችቷል ፡፡ አንድ ሰው በእውነት በአላህ ካመነና ጥሩ ሥራን ለመስራት ከሞከረ አላህ እምነቱን የሚያጠናክርበትና ጥሩ ሥራውን የሚጨምርበት ሁኔታ ያመቻችለታል።

« ወደ እናንተ አብራሪ የኾኑን
አንቀጾች ከነዚያ ከበፊታችሁ ካለፉትም
(ምሳሌዎች ዓይነት) ምሳሌን ለጥንቁቆች
መገሰጫንም በእርግጥ አወርድን ። »

(ቅ.ቁ 24:34)

ፈጣሪ የሌላት ሁለንተናዊ ዓለም ድቅድቅ ጨለማ ናት ፡፡ ቅዱስ ቁርአን እንዲህ ይላል፡-

« እነዚያ የካዱት ሰዎች ሥራዎቻቸው
(መልካሞቹ) በበረሃ ሜዳ እንዳለ ሲራብድ

የጠማው ሰው ውሃ ነው ብሎ እንደሚያስበው
በመጣም ጊዜ ምንም ነገር ኾኖ
እንደማያገኘው ነው (ከሐዲው) አላህንም
እስራው ዘንድ ያገኘዋል ። ምርመራውንም
(ቅጣቱን) ይመለከታል ፡፡ አላህም
ምርመራው ፈጣን ነው ። ››
‹‹ ወይም (መጥፎ ሥራዎቻቸው) ከበላዩ
ማዕበል ከበላዩ ደመና ያለበት ማዕበል
በሚሸፍነው ጥልቅ ባህር ውስጥ እንዳሉ
ጨለማዎች ነው ፡፡ (እነዚያ) ከፊላቸው
ከከፊሉ በላይ ድርብርብ የሆኑ ጨለማዎች
ናቸው (በዚህች የተሞከረ ሰው) እጁን
ባወጣ ጊዜ ሊያያት አይቀርብም ።
አላህም ለርሱ ብርሃንን ያላደረገለት ሰው
ለርሱ ምንም ብርሃን የለውም ። ››

(ቅ.ቁ 24፡39-40)

ኢስላም ስለፈጣሪ (አላህ ሱ.ወ) ያለው አመለካከትና የቁርአን ጽንሰ ሐሳብ በነዚህ ላይ የተመሰረተ (ያረፈ) ነው ።

1. አላህ አምሳያ የሌለው፣የተብቃቃ አጋር የሌለው የነበረና ወደ ፊትም የሚኖር አንድና ሸሪክ የሌለው ነው ።

(ቅ.ቁ 112፡4)

2. ከዚህ በታች በአንቀጽ አራት (4) ሲገልጽ እንዲህ ይላል ፡፡

« ለእርሱ አንድም ብጤ የለውም ፡፡ »

በዚህች ዓለም ላይ ምንም ነገር ያልነበረ ሲሆን አላህ ብቻውን ሁሉንም አስገኛቸው በሚል መሰረታዊ ጽንሰ ሃሳብ ላይ የተመሰረተ የተውሂድ ክፍልን ሙስሊም በፀና ያምናል ፡፡ አላህ ከፍጥረታት ምንም ነገር ሳይፈልግ ፍጥረትን ጠብቆ ያቆያል ፡፡ እርሱ የዩኒቨርሰና በውስጧ ለሚኖሩት ሁሉ ብቸኛ ጌታና ለጌትነቱ እውነተኛ ተቀናቃኝ የሌለው ነው ፡፡ ይህ የተውሂድ ዘርፍ የሚያስገነዝበን አላህ ብቸኛና እውነተኛ ሀይል እንደ መሆኑ ለሁሉም ነገሮች እንዲንቀሳቀሱና እንዲለወጡ ሀይል የሚሰጠው እርሱ ነው ከእርሱ ፈቃድ ውጭ ምንም ነገር የሚሆን እንደሌለ ነው፡፡ አላህ ከሁሉም በላይ ሃያል ነው ፡፡ ፍጡራን ከርሱ ጋር የሚነፃፀር ሃይል የላቸውም ፡፡ ኢምንት ናቸው ፡፡ እጣ ፈንታቸው ሁሉ በእጁ ነው ፡፡ እርሱ የፈቀደው ብቻ ነው እውን የሚሆነው እቅዱና ፍላጎቱን የሚያደናቅፍበት ኃይል የለም ፡፡ እርሱ ያልፈቀደው ነገር ደግሞ ሊፈፀም አይችልም ፡፡

« አላህ ምንም ልጅ አልወለደም፤ከእርሱ ጋር አንድም አምላክ የለም ፡፡ ያን ጊዜ

(ሌላ አምላክ በነበረ) አምላክ ሁሉ
በፈጠረው ነገር በተለየ ነበር ፡
ከፊላቸው በከፊሉ ላይ በላቀ ነበር ።
አላህ ከሚመጥኑት ሁሉ ጠራ። ››

(ቅ.ቁ 23፡91)

‹‹ በሁለቱ (በሰማያትና በምድር) ውስጥ
ከአላህ ሌላ አማልክት በነበሩ ኖሮ
በተበላሹ ነበር ። የዐርሹ ጌታ አላህም
ከሚሉት ሁሉ ጠራ ። ››

(ቅ.ቁ
21፡22)

3. አላህን በስልጣኑ የሚጋራ የለም ። አላህ ገደብ የለሽ ሥልጣን ያለው ነው።

‹‹ በምድር ላይ ሂዱ መፍጠርንም
እንዴት እንደ ጀመረ
ተመልከቱ፤ከዚያም አላህ
የመጨረሻይቱን መነሳት
ያስነሳናል፤አላህ በነገሩ ሁሉ
ላይ ቻይ ነውና በላቸው ››

(ቅ.ቁ 29:20)

4. አላህ ሁሉን አዋቂ የሆነ ጌታ ነው ።

‹‹ አላህም ሕዝቦችን ከአቀናቸው በኃላ የሚጠነቀቁትን (ሥራ) ለነሱ እስከሚገልጽላቸው (እስከሚተውትም) ድረስ ጥፋተኛ የሚያደርግ አይደለም ። አላህ በነገሩ ሁሉ አዋቂ ነውና። ››

(ቅ.ቁ 9:115)

5. አላህ እጅግ በጣም አዛኝ በጣም ሩህሩህ የሆነ ጌታ ነው ። የአላህን በጎ አድራጊነት (ኢሕሳን) ቸርነት እዝነት‧ና ርህሩህነት የሚያመለክቱ ስሞች ደግሞ

"ራሕማን" በሚለው ስሙ ሥር የሚካተቱ ናቸው ። ከሱራ 9 በስተቀር ሁሉም የቁርአን ሱራዎች የአላህን እዝነት፣የአላህን ቸርነትና ሩህሩህነት ይገልፃሉ ። (በዚህ ይጀምራሉ።)

(ቅ.ቁ 12:46)

በቁርአን በነብዩ ሐዲስ የአላህን ታላቅነትና ውበት (ሲፋት አልጀሊል ወል ጀማል) የሚያመለክቱ ስሞች በሙሉ "አላህ" በሚለው ስሙ የሚካተቱ ናቸው ። የአላህ ትዕዛዝ ያለማክበር ከመንገዱ መውጣት የሚያስከትለውን ቅጣትና በወዲያኛው ዓለም የፍርድ ቀን ከሃዲዎች የሚደርስባቸውን ሁሉ ቅጣት በማሰብና በመጨነቅ የአላህን እዝነት ይፈልጋሉ ። የጀነትን ምንነት ምቾትና ደስታውን በማሰብ ደግሞ የአላህን ቸርነትና ሩህሩህነት ለእነርሱ እውን እንዲያደርግላቸው ይለምናሉ ።

‹‹ ባሮቼም ከኔ በጠየቁ ጊዜ (እንዲህ በላቸው) እኔ ቅርብ ነኝ የለማኝን ፀሎት በለመነኝ ጊዜ እቀበለዋለሁ ። ስለዚህ ለኔ ይታዘዙ በኔም ይመኑ እነሱ ሊመሩ ይከጀላልና ። ››

(ቅ.ቁ 2:186)

አላህ (ሱ.ወ) የሁሉ ነገር ፈጣሪ ነው። ሁለንተናዊ ዓለምን የፈጠረና የሚያቆይ ሲሆን ዓለምም ስትጠፋ እሱ ዘላለማዊ ኗሪ ነው ። በየወቅቱም ሁሉ ነገር ሥርዓቱን ጠብቆ እንዲንቀሳቀስና መጥፋት ካለበትም እንዲጠፋ አድራጊው አላህ ነው ። ይህንም በተመለከተ ቅዱስ ቁርአን እንዲህ ይላል ።

‹‹ በሰማያትና በምድር ውስጥ
ያሉት ሁሉ ይለምኑታል በየቀኑም
ሁሉ እርሱ በሥራ ላይ ነው ። ››

(ቅ.ቁ 55፡29)

የአላህን ባህሪያት በቁርአን እንደተገለጸው በዚህ መልክ (ከዚህ በታች በሱረቱል አል አሽር እንደተቀመጠው ነው ።

‹‹ እርሱ አላህ ነው፤ያ ከርሱ በቀር ሌላ
አምላክ የሌለ ሩቁንና ቅርቡን
አዋቂ የኾነ ነው ፤እርሱ እጅግ በጣም
ሩህሩህ በጣም አዛኝ ነው ። ››
‹‹ እርሱ አላህ ነው ያ ከርሱ በቀር ሌላ
አምላክ የሌለ ንጉስ ከጉድለት
ሁሉ የጠራ የሠላም ባለቤት ፤ጸጥታን
ሰጪው፤ባሮቹን ጠባቂው፣ አሸናፊው፣
ሃያሉ፣ ኩሩው ነው ፤አላህ ከሚያጋሩት ሁሉ
ጠራ።
‹‹ እርሱ አላህ ፈጣሪው (ከኢምንት)
አስገኚው ቅርጹን አሳማሪው ነው ።
ለርሱ መልካሞች ስሞች አሉት፤

በሰማያትና በምድርም ያለው ሁሉ

ለርሱ ያሞግሳል፤ እርሱም አሸናፊው

ጥበበኛው ነው ። ››

(ቅ.ቁ 59፡22-24)

## 3.2 *ነብይነትና መገለጫዎቹ*

በኢስላም ዕምነት ሁለተኛውና መሰረታዊ መርህ ነብይነትና መገለጫዎቹ (ወህይ) ሲሆን ከፍተኛ የሆነ ጠቀሜታ አለው ። የሰው ልጅ ያለ ነብዮች አመራር በራሱ አእምሮና የአስተሳሰብ አድማስ የፍጡራንን የመጨረሻ ዓላማ ለማወቅ በፍጹም አይቻለውም ። በመሆኑም ፈጣሪው (አላህ) በየዘመኑ ነብዮችን ከህዝቡ መሃል በመምረጥ ይሾማቸዋል። ነብዮችም እንደየዘመናቸው እና እንደ ህብረተሰቡ ሁኔታ በተሰጣቸው መለኮታዊ መጽሐፍት መሰረት ህዝቦቻቸውን ይመራሉ ። በቅዱስ ቁርአን እንደተገለጸው የሰው ልጅ ታሪክ ከተጀመረ ጀምሮ አላህ (ሱ.ወ) ከአደም (ዐ.ሰ) ጀምሮ ሙሳን (ዐ.ሰ) እና ኢሳን (ዐ.ሰ) እንዲሁም የማጠቃለያውን ነብይ መሃመድ (ሰ.ዐ.ወ) የሰው ልጆች ወደ ትክክለኛ አቅጣጫ እንዲመሩ መርጧቸዋል ። ነብዩ መሐመድን (ሰ.ዐ.ወ) የሃይማኖቶች ሁሉ ማጠናቀቂያ የሆነው ኢስላምን እንዲያስተምሩ የተአምራቶች ሁሉ ተአምራት የሆነውን መለኮታዊ መጽሐፍ፣ ቅዱስ ቁርአንን

አውርዶላቸዋል ። ነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ለአንድ ጎሳ ሳይሆን ለዓለም ህዝቦች ሁሉ የተላኩ ነብይ ናቸው ። ቁርአንም የአለም ብርሃን ሲል አወድሷቸዋል ።

*ነብዮችን በተመለከተ የሚያብራሩ ነጥቦች*

1) ነብዮች ሁሉ ሰዎች ናቸው ፤የሰው ባህርይ የተላበሱ ናቸው፤እንደ ሰው ይበላሉ፣ይጠጣሉ፣እንደ ሰው ይኖራሉ ። ቅዱስ ቁርአን ይህን በተመለከተ በአንቀጽ 7 ሱራ 25 እንዲህ ይላል ።

« ለዚህም መልዕክተኛ ምግብን የሚበላ፤ በገቢያዎችም የሚሄድ ሲሆን፣ ምን መልዕክተኛነት አለው? ከርሱ ጋር አስፈራሪ ይሆን ዘንድ
ወደርሱ መልአክ (በግሃድ) አይወርድም ኖሯልን? አሉ ። »

(ቅ.ቁ 25፡7)

ነብዮች የሚታዩ፣የሚጨበጡ እንደ ሰው አካልና መጠን ያላቸው ምርጥ የአላህ ባሪያዎች ናቸው ።

2) ምንም እንኳን ነብዮች በአላህ (ሱ.ወ) ተመርጠው የተሰየሙ ይሁኑ እንጂ በተፈጥሯቸውም ከሰው ልዩ የሚያደርጋቸው መልካም ባህያት አሏቸው። እነዚህም መልካም ባህያትና መለያቸው ከመለኮታዊ ዓለም ጋር በቀጥታ የሚያገናኟቸው ሲሆኑ የአላህም ተአምርና ወሳኝነት በተሰጣቸው ብቃትና ተአማኒነት ከአላህ ወደ ሰው (ፍጡራን) የሚያደርሱ እውነተኛ የአላህ ባሪያዎች ናቸው ።

3) ሁሉም በአላህ የተሰየሙና የተሾሙት ነብዮች አንድ አይነት መለኮታዊ ደረጃ የላቸውም። አንዱ ከሌላው የሚበልጥባቸው ሁኔታዎች አሉ ።

4) ምንም እንኳ ከአላህ (ሱ.ወ) የተሾሙና የተሰየሙ ቢሆንም እያንዳንዳቸው ለተላኩበት ዘመንና ህዝብ በወቅቱ በተሰጣቸው መንፈሳዊ ደረጃና መለኮታዊ ነብይነት ብቻ የተወሰኑ ናቸው ። ስለዚህ እነዚህ መለኮታዊ ነብዮች በቋንቋ ይለያያሉ ። በቋንቋ መለያየታቸው ግን ተልዕኮአቸውን አያለያየውም ሁሉም የተላኩት የአላህን አንድነት ለማስተማር ነው ።

ቅዱስ ቁርአን ሃይማኖትን ሲገልፅ በነጠላ ቃል ነው ። ይህም የሚያመለክተው ከመጀመሪያው ነብይ አዳም (ዐ.ሰ.) እስከ ማጠናቀቂያው ነብይ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ)

ድረስ ያለው ተልዕኮ አንድ ዓይነት መሆኑን ነው ። በመሆኑም እያንዳንዱ ነብይ በዘመኑ የሚቀጥለውን ነብይ ማንነት እየገለጸ ነው የራሱን የነብይነት ዘመን የሚያጠናቅቀው። ቅዱስ ቁርአን ሁሉም ነብዮች የአላህ አገልጋዮች ናቸው በማለት ነው የሚጠቅሰው ስለሆነም ሁሉም ሙስሊሞች ናቸው ። ሙስሊም ማለት ለአላህ ያደረ ፣ለፈጣሪው በፍፁምነት የሚገዛ ማለት ነው ።

## 3.3 በመላኢካዎች ማመን

በማይታዩት ነገሮች ማመን ስንል የምጽአትን ቀን (የቂያም ቀን) የመጽሐፍትን (የቅዱስ) መውረድ፣እና መለኮታዊ ነብያትን በተመለከተ ሲሆን ቁርአን ደግሞ ስለ መላኢካዎች መኖርና ስለ ሚያከናውኑት ተግባርና ዕምነት በተጨማሪ ያረጋግጥልናል። በመሆኑም በመላኢካዎች ማመን ለአንድ ሙስሊም ግዴታው ነው። መላኢካዎች የአላህን ትዕዛዝ ለፍጡራን በማድረስ መለኮታዊ ተግባርን የሚፈፅሙ የማናያቸው የአላህ ባሪያዎች ናቸው ። ከመላኢካዎች ውስጥ ጂብሪል (ገብርኤል) የተባለው መላኢካ በአላህና በሰው ልጅ መሪ በሆኑት ነብዮች መካከል ትዕዛዝን የሚያስተላልፍ ሲሆን፣ኢዝራኢል ደግሞ የሠዎችን ነፍስ ከስጋቸው የሚለያይ የሞት መልአክ ነው። የሰዎችን መልካም

ሥራና መጥፎ ተግራትን የሚመዘግቡ መላኢካዎችም አሉ ፡፡

እንደ ኢስላማዊ አመለካከት የመላኢካዎች ደረጃ ከአላህ ያላቸው ቅርበትና ርቀት ይለያያል ፡፡ አርሽን (መለኮታዊ ዘፋንን) ቀጥ አድርጎ ተሸክሞ ከቆመው መላኢካ እስከ የተለያዩ መለኮታዊ መልዕክቶችን ከፈጣሪ ወደ ፍጡራን የሚያደርሰው ድረስ ያሉት በደረጃ ይለያያሉ ፡፡ ከአላህ (ሱ.ወ) መለኮታዊ ግርማ የተባረሩት ኢብሊሶችን (ሰይጣኖችን) ጨምሮ ፡፡ ኢ.ብሊስ ከመለኮታዊ መላኢካዎች አንዱ ነበር ፡፡ ነገር ግን በሰራው ጥፋት ክብሩ ተዋርዶ የሰውን ልጆች በማሳሳት ሂደት ላይ ዝንት አለም እንዲቆይ ሆኗል፡፡ ኢብሊስ ከአላህ ክብርና ሞገስ ፊት እንዲባረር የተደረገው መለኮታዊ ትዕዛዝን አልቀበልም በማለቱ ነው፡፡ ይኸም ለአዳም (ዐ.ሰ) አልሰግድም ብሎ በማመጹ ምክንያት ነው ፡፡

## 3.4 የሠው ልጆች ደረጃ

የሰው ልጆች በቅዱስ ቁርአን የተከበሩና የላቁ ፍጡሮች ተደርጎ ይነገራል ፡፡ በምድር ላይ የፈጣሪው ኸሊፋ ሆኖ ሃላፊነት ተሰጥቶታል ፡፡ የሰው ዘር አዳም ከጀነት ከወጣና መሬት ላይ መኖር ከጀመረ ወዲህ ተጠያቂ አድርጎታል ፡፡ በቅዱስ ቁርአን ላይ እንደተጠቀሰው የአዳም አፈጣጠር ቀስ በቀስና ደረጃ በደረጃ ነው፡፡ ሥነ ልቡናና

ቁስአዊ ሂደቱን ስንመለከት አዳም መለኮታዊ ስትንፋስ የተተነፈሰበት ፍጡር ነው ። ለዚህም ምዕራፍ 22 አንቀጽ 5 እንዲህ ይላል ።

« እናንተ ሰዎች ሆይ ! ከመቀስቀስ፤
በመጠራጠር ውስጥ እንደሆናችሁ
(አፈጣጠራችሁን ተመልከቱ)፤
እኛም ከአፈር ፈጠርናችሁ ፤ከዚያም
ከፍትወት ጠብታ፣ከዚያም ከረጋ ደም፣
ከዚም ከቁራጭ ሥጋ ፍጥረትዋ
ሙሉ ከሆነችና ሙሉ ካልሆነች(ችሎታችንን)
ለናንተ ልንገልጽላችሁ ፈጠርናችሁ፤
የምንሻውንም እስከ ተወሰነ ጊዜ ድረስ
በማህፀን ውስጥ እናረጋዋለን፤ ከዚያም
ህጻን ሆናችሁ እናወጣችኋለን ፤
ከዚያም ሙሉ ጥንካሬያችሁ ትደርሱ
ዘንድ (እናሳድጋችኋለን) ከናንተም
የሚሞት ሰው አለ ፤ ከእናንተም
ከዕውቀት በኋላ ምንንም እንዳያውቅ
ወደ ወራዳ እድሜ የሚመለስ ሰው አለ፤
ምድርንም ደረቅ ሆና ታያታለህ፤
በርሷም ላይ ውሃን ባወረድን ግዜ
ትላወሳለች፤ትተነፍሳለችም፤ውበት

ካለው ጎሳ ሁሉ ታበቅላለችም። ››

(ቅ.ቁ 22፡5)

አዳምን መለኮታዊና የላቀ ፍጡር ስናደርገው መላኢኮችም እንዲሁ እንዲሰግዱለት አዘዝናቸው ። ሁለንተናዊ ዓለም በርሱ ሥር እንድትውል አደረግንም፤በማለት አላህ (ሱ.ወ) የተናገረውን በምዕራፍ 38፡72-73 ያለውን እንመልከት ።

‹‹ ፍጥረቱንም ባስተካከልኩና ከመንፈሴ በነፋሁበት ጊዜ፤ ለርሱ ሰጋጆች ሆናችሁ ውደቁ (አልኩ) ። መላዕክትም መላውም በአንድነት ሰገዱ ። ››

(ቅ.ቁ 38፡72-73)

አዳም የተከለከለውን የገነት ዛፍ ፍሬ በመቅመሱ አላህ (ሱ.ወ) ከገነት (ጀነት) አስወጣው። ይህ እምቢተኝነቱ፣አልታዘዝ ባይነቱ፣የነጻነቱ ምልክት ነው ። አዳምን. ከሌሎቹ መላኢኮች የላቀ ያደረገው በአካባቢው ያለውን ነገር ማወቅና መለየት የሚችል በመሆኑ ነው። አዳም ከገነትም ሲወጣ በምድር ላይ ግሮ ጥሮ እንዲበላ አደረገው ። ትውልዱም በግጭትና በጦርነት ውስጥ በመሆን

ራሱን እያስተካከለ ከሙስናና ደም መፋሰስ በመጽዳት ወደ ጌታው ይመለስ ዘንድ እድል ሰጥቶታል ።

ኢስላም የሰውን ልጅ ጠንቅቆ የሚያስብ ፣ነጻ እና አስተዋይ ፍጡር ነው ይለዋል ። በአንጻሩ ደግሞ አንዳንድ ክርስቲያን ምሁራን እንደ ቅዱስ አጉስቲን የመሳሰሉ የሰውን ልጅ ከተፈጥሮአዊ ወይም ከአዳም ስህተትና ወንጀል ጋር ያያይዙታል ። ኢስላም ይህን በተመለከተ ግልፅ የሆነ አቋም አለው ። ልጅ በአባቱ ሃጢአት ተጠያቂ አይሆንም ይላል ። ፈጣሪውንና ዕውነትን የመፈለግ፣ ጥሩውንና መጥፎን የማወቅ ችሎታ ታድሎታል ። በቅዱስ ቁርአን እንደሚታወቀው የአዳም ልጆች ወደዚች ዓለም ከመምጣታቸው በፊት ምንነታቸው በፈጣሪያቸው ዘንድ የታወቀ ነው ።

« ጌታህም ከአዳም ልጆች ከጀርባቸው
ዘሮቻቸውን ባወጣና ጌታቸው አይደለሁምን ?
ሲል በነፍሶቻቸው ላይ ባስመሰከራቸው ጊዜ
(የሆነውን አስታውስ) ጌታችን ነህ፤
መሰከርን፣አሉ፤ በትንሳኤ ቀን ከዚህ
/ኪዳን/ ዘንጊዎች ነበርን፤እንዳትሉ፤ »

(ቅ.ቁ 7፡172)

ፍጡራን ሁሉ ጌታቸውን /ፈጣሪያቸውን/ እንደሚፈልጉ ተፈጥሮአዊ የሆነ ምልክት አለው ። በተለይም ደግሞ የሰው ልጅ ፈጣሪውን የሚያውቅበት መለኮታዊ ሁኔታዎች አሉ። በመሆኑም የአንድ ትውልድ ፍጡር የሌላውን ትውልድ ሃጢአትና መከራ ተቀባይ የማይሆንበት ሁኔታ ስለመኖሩ ኢስላም አጥብቆ ያምናል ። ተፈጥሮአዊ ሃጢአት ተብሎ ነገር በኢስላም የለም። የሰው ልጅ ኃጢአት የሚጀምረው እያንዳንዱ ሰው ከዓለማዊ ተግባር ጋር በሚፈጥረው መስተጋብር ከመለኮታዊ ትዕዛዝና መመሪያ ሲወጣ ነው ። በመሆኑም ነብዮችና መለኮታዊ መጽሐፍት የሰውን ልጅ አስታዋሽ ናቸው ።

እንደ ቅዱስ ቁርአን የሰው ልጅ የሚከተሉት ተፈጥሮአዊ ባህሪያት አሉት ።

1. የሰው ልጅ ለፈጣሪው የቀረበ ፍጡር ሲሆን በሚኖርበት ዓለም ለኑሮ ይጠቀምበት ዘንድ ሁሉም ተመቻችተውለታል ። (70:19-35)

   « (መሃመድ ሆይ!) ጌታህ ለመላዕክት፤
   እኔ በምድር ላይ ምትክን አድራጊ ነኝ፤
   ባለ ጊዜ ፤(የሆነውን አስታውስ፤እነርሱም)
   እኛ ከማመስገን ጋር የምንጠራህ ላንተም

የምንቀድስ ስንኾን በርሷ ውስጥ የሚያጠፉንና ደሞችንም የሚያፈስን ታደርጋለህን? አሉ፤(አላህ) እኔ የማታውቁትን ነገር አውቃለሁ አላቸው ። ››

(ቅ.ቁ 2:30)

2. መለኮታዊ መንፈስ ባለው ፍጡር ላይ ተነፍቷል (35:72) በመሆኑም መለኮታዊ ፍጡር ነው ። (30:30) ስለዚህ ወደ ፈጣሪው ያዘነብላል ።

« ፍጥረቱንም ባስተካከልኩና ከመንፈሴ በነፋሁበት ጊዜ ለርሱ ሰጋጆች ኾናችሁ ውደቁ (አልኩ) ››

(ቅ.ቁ 38:72)

« ወደ እውነት ተዘንባይ ሆነህም ፊትህን ለሃይማኖት ቀጥ አድርግ፤ የአላህን ፍጥረት ያችን አላህ ሰዎችን በርሷ ላይ የፈጠረባትን (ሃይማኖት) የአላህን ፍጥረት መለወጥ የለም፤ይህ ቀጥተኛ ሃይማኖት

ነው፤ ግን አብዛኞዎቹ ሰዎች
አያውቁም ። ››

(ቅ.ቁ 30፡30)

3. የሰው ልጅ መለኮታዊ ሃላፊነትን ተሸክሟል ይህም የነጻነቱና የህሊናው ጉዳይ ነው ።(33፡72)

‹‹ እኛ አደራን በሰማያትና በምድር፤
በተራራዎች ላይ አቀረብናት፤
መሸከሟንም እንቢ አሉ፤
ከርሷም ፈሩ፤ሰውም ተሸከማት፤
እርሱ በጣም በደለኛ ተሳሳች ነውና፤››

(ቅ.ቁ 33፡72)

4. የሰው ልጅ ነጻ ምርጫ ተሰጥቶታል ፤ጌታውን (አላህን) የማምለክ፣ወይም ያለማምለክ፤
5. የሰው ልጅ መለኮታዊ ተፈጥሮ ይኑረው እንጂ በአንጻሩም አሉታዊ ባህሪያት አሉት ። ለምሳሌ ስስታምነት፣አላግባብ አባካኝነት፣ቁጡነት፣ ትዕቢትን የመሳሰሉ፤ሥለዚህ የሰው ልጅ ሁለት ገጽታዎች አሉት ማለት ይቻላል።

‹‹ ሰው ቅጠ ቢስ ሆኖ ተፈጠረ።

ከፉ ነገር ባገኘው ጊዜ ብስጭተኛ፡፡
መልካምም ነገር (ጸሎት) ባገኘው
ጊዜ ከልካይ (ሆኖ ተፈጠረ) ሰጋጆች
ብቻ ሲቀሩ እነዚህ እነርሱ
በስግደታቸው ላይ ዘውታሪዎች
የሆኑት እነዚያም በገንዘቦቻቸው ላይ
የታወቀ መብት ያለባቸው የኾኑት፡፡
እነዚያም በፍርድ ቀን እውነት
የሚሉት (የሚያረጋግጡት)፡፡ እነዚያም
እነሱ ከጌታቸው ቅጣት ፈሪዎች
የኾኑት፡፡ ››

(ቅ.ቁ 70፡19-35)

‹‹ ሰውንም ከኛ ችሮታን ብናቀምሰው
ከዚያም ከርሱ ብንወስዳት፤እርሱ
በእርግጥ ተስፋ ቆራጭ ክህደተ
ብርቱ ነው ፡፡ ካገኘችውም ችግር
በኋላ ጠጋዎችን ብናቀምሰው ችግሮች
ከኔ ላይ በእርግጥ ተወገዱ ይላል፤
(አያመሰግንም) እርሱ ተዳሳች ጉረኛ
ነውና፡፡ ግን እነዚያ የታገሱ መልካም

ሥራዎችንም የሠሩ እነዚያ
ለነርሱ ምህረትና ታላቅ ምንዳ
አላቸው:: ››

(ቅ.ቁ 11፡9-11)

6. የሰው ልጅ ውስን የሆነ የዕውቀት ደረጃ የለውም ዕውቀቱ ከነባራዊ ሁኔታ ጋር በተዛማጅነት እያደገ የሚሄድ በአላህ ፍቃድ የተመኘውንና ያሰበውን ለመስራት የሚችል ፍጡር ነው በኢስላም ውሳጣዊ ይዘት ከአካላዊ ሁኔታ በልጦ አይታይም:: እንደ ቅዱስ ቁርአን አገላለጽ የሰው ልጅ በጥረት እና ግረቱ የተመኘውን ማግኘት የሚችል ታላቅ ፍጡር ነው :: (53፡39)

‹‹ ለሰውም ሁሉ የሰራው እንጂ ሌላ
የለውም :: ››

(ቅ.ቁ 53፡39)

‹‹ የተጥራራ ሰው በእርግጥ ዳነ ››

(ቅ.ቁ 87፡14)

‹‹ እነዚያ ከበፊታቸው አገሪቱን

መኖሪያ ያደረጉት እምነትንም የለመዱት ወደ እነርሱ የተሰደዱትንም ሰዎች ይወዳሉ፤ (ስደተኞች) ከተሰጡትም ነገር በልቦቻቸው ውስጥ ቅሬታን አያገኙም በነሱ ላይ ችግር ቢኖርባቸውም በነፍሳቻቸው ላይ ሌላውን ይመርጣሉ የነፍሱን ንፍገት የሚጠብቅ ሰው፤እነዚያ እነሱ ምኞታቸውን አግኝዎች ናቸው ። ››

(ቅ.ቁ 59፡9)

## 3.5 ቁርአን

ቁርአን የሙስሊሞች መለኮታዊ መጽሐፍ ነው ። ቁርአን ትክክለኛ መለኮታዊ መጽሐፍ ሲሆን ከአላህ ለነብዩ መሐመድ(ሰ.ዐ.ወ) የተወረደ ነው ። ቁርአን ከሌሎች መለኮታዊ መጽሐፍት ልዩ የሆነባቸው መሰረታዊ ጉዳዮች የሚከተሉት ናቸው።

1) ቁርአን የመለኮታዊ መጽሐፍ መደምደሚያ ቅዱስ መጽሐፍ ነው ። የሰው ልጆች በዚህ ሙሉ (እንከንየለሽ) መጽሐፍ ይመሩ ዘንድ ከፈጣሪ የተሰጠ ነው ።
2) ቁርአን የዘለዓለም ሕይወት መመሪያ ብቻ ሳይሆን የነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ተአምርም

ነው ። የሰው ልጅ አእምሮ ሊያዘጋጀው ሊጽፈው የማይችል ይዘትና ቅርጽ ያለው ከመሆኑም በላይ ቁርአን ሲነበብ የሚሰማ ሁሉ የመረጋጋትና የደስታ መንፈስ ያድርበታል ። ቁርአን የወረደበት ሁኔታና የተቀነባበረበት ዘዴ ሁሉ ከመለኮታዊ ኃይል ጋር ግንኙነት ስለአለው የሚሰለች አይደለም።

3) ለሙስሊሞች ቁርአን ሁሉም ነገሩ መለኮታዊና ቅዱስ ነው ። ፊደሎቹ፣ቃላቶቹ እና ጥንቅሩ እና በአጠቃላይ ይዘቱ የላቀ መንፈሳዊ መልዕክት መለኮታዊ ብስራት ያለው ነው ።

4) ቁርአንን በተመለከተ በሙስሊሞች መካከል ልዩነት የለም ። ሁሉም የአላህ መልዕክትነቱን ያረጋግጣሉ። ምንም እንኳን ሙስሊሞች የተለያዩ አስተሳሰብ ውጤቶች ቢሆኑም የቁርአንን የአላህ ቃልነት በተመለከተ ቃላቸው አንድ ነው። አላህ (ሱ.ወ) ለነብዩ መሐመድ የሰውን ልጅ ይመሩበት ዘንድ ያወረደው ለመሆኑ በመካከላቸው ቅሬታ ወይም ልዩነት የለም ። በመሆኑም በየትም ዓለም ሙስሊሞች ባሉበት ብትሄዱ የምታገኙት ያው አንድ ዓይነት የሆነውን ቁርአንን ነው ።

5) ቁርአንን ከሌሎች ጽሑፎች ልዩ የሚያደርገው ግልጽ የሆነ ታሪክ ያለው መሆኑ ነው። አጀማመሩና አጨራረሱ፤የመጀመሪያና የመጨረሻ ጥቅሶቹ (አያዎች) እና የምዕራፎቹ አቀማመጥ በሚገባ በተስተካከለ መንገድ መሆናቸው ነው ።

ቁርአን በ23 ዓመት ውስጥ የተወረደ ነው። የመጀመሪያው የቁርአን ምዕራፍ (ምዕራፍ96) በሜካ በአል-ኑር ተራራ የወረደ ሲሆን በዚህ ወቅት ነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የ40 ዓመት ሰው ነበሩ ። አል-ዐለቅ (የረጋ ደም ምዕራፍ) በመካ የወረደች ናት አያትዋ (አንቀጾችዋ) 19 ናቸው ። የመጨረሻው ምዕራፍ የወረደው ነብዩ 63 ዓመት በነበሩበት ወቅትና ከመሞታቸው በፊት ነበር። የቁርአን ምዕራፎቹ አወራረድ ቀስ በቀስ ሲሆን ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በተለያዩ ሁኔታዎች ላይ እያሉ የሚወርዱ ነበሩ።

ለምሳሌ ነብዩ በጉዞ ላይ እያሉ (በእግራቸው) በግመል ጀርባ ላይ ሆነው ከሰዎች ጋር እየተነጋገሩ ባሉበት ሁኔታ ሲሆን በዚህ ጊዜ ሰሐባዎች የነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) ሁኔታ በጽሞና ይከታተላሉ ። ከነብዩ የሚሰሟቸውን ቃላት በመማር እንደ አስፈላጊነቱ ያስታውሳሉ ።

ነብዩ መሐመድ ሲሞቱ ቁርአንን በቃሉ ያጠናው ሙስሊም ቁጥር መቀነስ ጀመረ። ይህን ሁኔታ የተመለከቱ ሙስሊሞች ፈጥነው በመጽሐፍ መልክ እንዲቀመጥ አደረጉ

። በመሆኑም ወህይ በወረደበት ወቅት ይሰበስቡና ይጽፉ ከነበሩት ሙስሊሞች መካከል እንደነ አሊ ኢብን አቡ ጣሊብ እና ዘይድ ኢብን ሳቢት በነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ጊዜ የሰበሰቡትን በማጠናቀር በኋላ በሦስተኛው ከሊፋ በዑስማን ዘመን በመጽሐፍ 114 ምዕራፎችን አካቶ ነብዩ ቀደም ሲል ባሳኩት መልክ ተደራጀ ። በትክክል የተጠረዘው የቁርአን መጽሐፍ ትክክለኛ ግልባጭ (ኮፒዎቹ) ለሁሉም ሙስሊም አገሮች ተላከ ። በዚህ አንድ ወጥ በሆነ ቁርአን ላይ ሁሉም ሙስሊም ያለ ልዩነት ይስማማበታል ። ይህ መጽሐፍ ፉርቃን ተብሎም ይጠራል ። ዑሙል ኪታብም ይባላል ። በሚሠጠው አመራርም ሁዳ ይሰኛል ።በሚሰጠው እውቀትና ብልሃትም አል-ሐኪም (ብልሃት) ተብሎ ይጠራል ።

ቁርአን ከአላህ ጋር ለሚደረግ ግንኙነት እንከን የለሽ ቅጽ ነው ። ለነብዩ መሐመድ በሕይወት ዘመናቸው በ23 ተከታታይ ዓመታት ውስጥ የተወረደ ሲሆን እስከ ዛሬ ድረስ በቁርአን ላይ ምንም ዓይነት ልዩነት በሙስሊሙ ህብረተሰብ ውስጥ በጭራሽ አይታይም ። ቁርአን 30 ጁዝ (ክፍሎች) 114 ምዕራፎች እና 6232 አንቀጾች አሉት። የአላህ ቃል እንደመሆኑ እያንዳንዱ አንቀጽ (አያ) በተናጠል አይተረጎምም ። ተገቢውን መልዕክት ለመረዳት እንዲቻል ተያያዥነት ባለው መልኩ ይተረጎማል ።

ቁርአን ሲወርድ በቅደም ተከተል አሁን ባለበት ሁኔታ የተወረደ አይደለም ።እንደ ርዝማኔውና ስፋታቸው መጠን የተጠናቀሩት በኋላ ነው ። የፋቲሃ ምዕራፍ ግን የመጀመሪያ ምዕራፍ በመሆን 7 አንቀጾች አሏት ። የመጨረሻው ደግሞ ስለ ሰው ልጆች የሚያወሳው ባለ 6 አንቀጽ ነው ። በመካ የወረዱት የመካ ሱራ ተብለው ሲጠሩ በመዲና የወረዱት ደግሞ የመዲና ሱራ ይባላሉ ። እነዚህም የመካና የመዲና ሱራዎች ተለያይተው አልተዘጋጁም ። በአንድ ላይ ናቸው ።

የሰው ልጅ ወደ ፈጣሪው የሚቃረብበትን በተመለከተ በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ መንገድ ያለውን ሁኔታ ቁርአን በተለየ ክስተቶች ይገልጸዋል። ጠቃሚ የሆኑትን ግንኙነት በተመለከተ ከዚህ እንደሚከተለው አጽንኦት ሰጥቷቸዋል ።

ሀ. ወደ ፍጹም ዘላለማዊ ተወዳጁ አምላክ (ማመላከት)

ለ. ከፊት ለፊቱ ፈጣሪው እንደሚታየው አድርጎ ለጸሎት መቆም

ሐ. ወደ ፈጣሪው መንገድ በፍቅር (በፍላጎት) ማየት

መ. መሰናክሎችን መለየት ማወቅ ።

በዚህ ጊዜ ልቦናንና አካልን አንድ አድርጎ ወደ ፈጣሪ በሚደረግ የቅርርብ ጉዞ ቁርአን ብቸኛ መለኮታዊ ተጠቃሽ መጽሐፍ ነው ። ቁርአንን ማንበብ ማስተንተን

መልዕክቱን በግልጽ ማወቅና የአላህን ቀጥተኛ አመራር ለማግኘት መጣር ነው።

የቁርአን አስተምህሮት በሦስት መሰረታዊ ጉዳዮች ሊከፈል ይችላል ። እነዚህም ፦

1 የእምነት መመሪያ

2 የሥነምግባር እና

3 ታሪካዊ በመባል ።

*1. የእምነት መመሪያ*

ኢስላም ማለት የአላህን አንድነት ማረጋገጥ ለእርሱ መታዘዝ ማለት መሆኑን አይተናል ። በዚህ የኢስላም ትርጉም መንፈስ ቀደም ሲል የነበሩት ነብያት ሁሉ የአላህን አንድነት የሚያረጋግጡ ለርሱ የሚታዘዙ ሙስሊሞች እንደነበሩ ተገንዝበናል። ከዚህ የምንማረው ነብዩች ሁሉ ሙሉ በሙሉ .ወደ አላህ አንድነት ወደ ተውሂድ ጥሪ የሚያደርጉ መሆናቸውን ነው ።

አላህ ከነቢያት አንዱንም ወደ ተውሂድ ጥሪ የሚያደርግ ቢሆን እንጂ ያልላከ መሆኑን ቁርአን ይነግረናል።

ኢስላም በአምስት አምዶች ላይ ተመሥርቷል። ከአላህ በስተቀር ሌላ አምላክ እንደሌለ መመስከርና መሐመድ የአላህ መልዕክተኛ መሆናቸውን መመስከር፣

ሶላትን አስተካክሉ በወቅቱ መስገድ፣ዘካትን ለሚገባቸው መስጠት፣ ሐጅ ማድረግና የረመዳንን ወር መጾም በማለት ነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ገልጸዋል ።

በአላህ ፣ በመላኢካዎቹ፣ በመጽሐፎቹ፣ በመጨረሻው ቀን ማመንና መልካምም ሆነ መጥፎው ሁሉ በቀድር (በአላህ ውሳኔ) የሚሆን መሆኑን ማመን ነው ።

*2. ሥነ ምግባር*

ቁርአን ማረጋገጫን ብቻ የሚያቀርብ መጽሐፍ ብቻ አይደለም ነገር ግን ይህን አታርግ ይህን አርግ የሚሉ ከሥነ ምግባር ጋር የተያያዙ መመሪያዎችም አሉት ። የሰው ልጅ በሕይወት ዘመኑ የሚመራባቸውን አንቀጾች ግልፅ በሆነ መንገድ አትቷል ። ሁሉም ነገር የተወሰነለትና የተመጠነለት ልክ አለው ። ከመጠኑም አያልፍም።

*3. ታሪካዊ ሁኔታ*

ቁርአን ታሪካዊ ሁኔታውን ስንመለከት በምሳሌ የአገላለጽ ጥበብ ለግሳጼ፣ለምክክርና ለማስተዋል በተጨባጭ መልክ ይበልጥ ለአእምሮ ለማቅረብ ለማነጻፀር የተጠቀመበት ሲሆን ይህ ዓይነቱ አገላለፅ የተፈለገውን ሃሳብ በልቦና ለማጽናት ግንዛቤን ለማጠናከር ውጤታማ ጥበብ ነው ።

‹‹ በዚህ ቁርአን ውስጥ ለሰዎች ይገልጹ ዘንድ ከየምሳሌው ሁሉ በእርግጥ አብራራን ። ››

የቅዱስ ቁርአን የአቀራረብ ስልት ምጥቀትና ጥልቀት በሥነ ጽሁፍና በሃይማኖት ዓለም አቻ የማይገኝለት በመሆኑ ታላላቅ የሥነ ጽሁፍ ሰዎች ባንድ ቃል መስክረዋል ። ቁርአን ብቸኛው የመሐመድ ተአምር ነው ። የተራቀቀው ሥነ ጽኁፋዊ ውበትና አንጸባራቂው ሃይሉ ያልተፈታ ምስጢር ሆኖ ዛሬም እንዳለ ሲሆን የሚያነበው ሰው አነስተኛ የአላህ ፍራቻ ካላቸው ሰዎች እንኳን ቢሆን ልዩ በሆነ የስሜት መቀስቀስ ሁኔታ ውስጥ ይዳረጋል ።

ከነብዮች መካከል በቅዱስ መጽሐፍ ተደጋግመው የሚጠቀሱት ኢብራሂም (አብርሃም)፣ሙሣ (ሙሴ) እና ኢሣ (ኢየሱስ) ናቸው ። በቁርአንም እነዚህ ነብዮች ተደጋግመው ይነሳሉ ። ኢብራሂም (ዐ.ሰ) ልጁን እስማኤልን ለአላህ ሲል ለመሰዋእትነት አቅርቦት ነበር ። እንደዚህ መሰሉን ታሪክ በቁርአን ማንበብ ማለት ለአማንያን የመንፈስ ብርታት ይሰጣል ። ተራ ለሆነ መረጃ ብቻ ሳይሆን ዓላማው መንፈሳዊና ሞራላዊ ምሳሌ በትረካ መልክ ለማቅረብ ነው ።

የቁርአን ተርጓሚዎች ጉዳዩ ይመለከተኛል ከሚል አቋም በመነሳት አንዳንዶቹ ሥነ ጽሁፋዊ ይዘቱን ሌሎች ደግሞ ይዘቱን ማዕከል በማድረግ ሰርተዋል ።

ዘማክህሻሃር ያዘጋጀው ከሺፍ የተባለው ከሥነ ጹኁፍ ሁኔታዎች አንፃር የተዘጋ ሲሆን ጠበሪና ኢማም ፈክር ራዚ "ተፍሲር አል ከቢር" (ታላቁ ትርጉም) በሚል ከሐይማኖቱ

አንፃር አዘጋጅተዋል ። ፍልስፍናዊ ትንተና በሙላ ሳድራ፣ከፈጣሪ ጋር ግንኙነት በሚመለከት ኢብን አረብ እና አብደላህ ኢንሳሪ፣ ሳይንሳዊ ወይም ማህበራዊ ጉዳዮችን ጠንጣዊ እና ሰይድ ቁጥብ በተቻለ መጠን የዳሰሱት ጉዳይ ነው ። ቁርአን ከሌሎች ሁኔታዎች አንፃር የሚታይበትን አል-ሚዛን ተባታባኢ አዘጋጅቶታል ። በተለያየ ዘመን የነበሩ ሙስሊሞች ቁርአንን በተመለከተ ከብዙ አንፃር አስተያየታቸውን ፅፈዋል ። እነዚህ ለየዘመናቸው የህይወት አካሄድ መመሪያና ደንብ ከመፈለግ አንፃር ቁርአንን መሰረት በማድረግ ብዙ ሥነ ጽሁፎችን አዘጋጅተዋል ።

የተለዩ የቁርአን ማብራሪያዎችና ጥያቄዎች ለምን ይነሳሉ ? አንድ ፍፁም የሆነ አገላለጽ ወይም ትርጉም ለምን አይኖርም? የሚል ሃሳብ ሊያስነሳ ይችላል ። በእርግጥ ትክክል ነው ። ነገር ግን ትርጉም ስንል ጠለቅ ያለ እውቀትና መረጃ አንድን ትርጉም ከሌለው ሊያበላልጠው ይችላል ። በመሆኑም ከተጨባጭ ሁኔታና ክስተት ጋር አብሮ ሊሄድ የሚችል መልስ ምንጊዜም ቢሆን ከቁርአን ይገኛል ። በዚህ ምክኒያት በአንድ ወቅት በተከሰተ ሁኔታና ድርጊት አንፃር የቁርአንን ፅንሰ ሀሳብ በመተንተን የሚሰጥ ትርጉም በሌላ ጊዜ ከሚመጣ ሁኔታ ጋር አንድ ባለመሆኑ ነው ። ቁርአን የሕይወት መመሪያ ነው ስንል የቁርአን አቀራረብ ስልት ከዘላለማዊ አሸናፊነቱ ባሕሪያት አንዱና

አስደናቂ የሆነው የአቀራረብ ሥልቱ ነው። ይህ ስልት በረቂቅነቱ፣ በውበቱ፣በአገላለፅ ብሩህነቱ ልዩ ባህሪያት አሉት ። ከዐረቦች የአነጋገር ስልትና የቅንብር ዘይቤ የተለየ ነው ።

### *3.6 የነብዩ ሐዲስ*

ሐዲስ የነብዩ ቃሎችና በሕይወት ዘመናቸው ኢስላምን በተግባር ላይ ሲያውሉ በተለያዩ አጋጣሚዎች የተናገሯቸው ንግግሮች ከፈጸሟቸው ድርጊቶችና ከሁኔታዎች የተጠናቀረ የቁርአን ማብራሪያ ነው ።

ነብዩ መሐመድ የአላህ መልዕክተኛ ቢሆኑም ሰው ናቸው ። ኢስላም ይህን በተመለከተ አጽንኦት ሰጥቶ ይገልፀዋል ። በእርግጥ ነብዩ መሐመድ ከጉድለት የጠሩ ሰው ነበሩ ። ከሰው ሁሉ በላጭ ሰው አድርጎ የፈጠራቸውም ለዓላማው አስፈፃሚነት ስለመረጣቸው ነው ። ለአላህ በጣም የቀረቡ፣ታላቅ ሃላፊነት የተቀበሉ የመልካም ሁሉ መገለጫ አድርጎ ፈጥሯቸዋል ። ቁርአን ነብዩን በሚመለከት እንዲህ ይላል ፦

‹‹ ለእናንተ አላህንና የመጨረሻውን ቀን
ለሚከጅል ለሆነ ሰው አላህንም
በብዙ ለሚያወሳ በአላህ መልዕክተኛ
መልካም መከተል አላችሁ ። ››

(ቅ.ቁ 33፡21)

ተወዳጅ ነብይ (ሰ.ዐ.ወ) ሩህሩህ ፣ታማኝ እና ትሁት ነበሩ ። በዚህም ምክኒያት የሚጠሉዋቸው ሳይቀሩ በመላው ይመሰክሩ ነበር ። አስተምሮአቸውና ግብረ ገባዊነታቸው በመላው የአረብ ሰላጤ ናኝቶ ነበር ። ነብዩ ሰዎችን መርዳት ቀዳሚ ተግባራቸው ሲሆን ከእምነት አንፃር እርሳቸውን ለተከተሉ ብቻ ሳይሆን ለሰው ልጆች ሁሉ መልካም መሥራትን ያዘወትሩ ነበር ። በሐይማኖቱም ትምህርት ሰዎችን ወደ ቀና መንገድ በመጥራት በኩል ታላቅ ተጋድሎ አድርገዋል ። ይህም እውነተኛ ተግባራቸው ነበር ሙሽሪክ አረቦችን ወደ ኢስላም ያመጣቸው። ሙስሊሙ ሕብረተሰብ ነብዩ መሐመድን የመውደድ ጉዳይ ከፍተኛ ቦታ የሚሠጠውና አብይ ሚና ያለው ነው። ይህንም ማለት የሳቸውን ምሳሌነት መከተል ግዴታም ስለሆነ ነው ። በ23 ዓመት የነብይነት ዘመናቸው በሰጡት አመራር፣ባሳዩት የማይለወጥ መልካም ጠባይ፣በውብና ማራኪ ንግግራቸው በአጠቃላይ በሁለንተናዊ ሥነ ምግባራቸው ዲናቸውን የተከተለ ይቅርና ከኢአማንያንም ቢሆን ፍቅር አትርፈዋል ። የነብዩ የግል ሕይወት ታሪክ (ሲራ) በእውነተኛ ዘጋቢዎች የተሰበሰበው በሐዲስ መልክ ይነገራል ። የሙስሊሞች ሱና ሆኖ በመቀጠል ላይ ይገኛል ። የነብዩን ታሪክ ማወቅ ለሁሉም ነገሮች ለሙስሊሙ ሕብረተሰብ ይጠቅማል ። አንደኛ ሙስሊሙ በሕይወቱ ውስጥ ለሚያደርገው

መስተጋብር ይረዳዋል ። ሁለተኛ ቁርአንን በአግባቡ ለመረዳት እና ለመተንተን (ለመፈሰር) ያግዘዋል ። የቁርአንን መልዕክት በቀጥታ ከአላህ የተቀበሉ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በመሆናቸው ቁርአንን በትክክል በመግለጽ ረገድ ከነብዩ ውጭ ሌላ አቻ ሊኖር ስለማይችል ነው ። ነብዩ የኢንፎርሜሽን ምንጭ ናቸውና።

ነብዩ ባለፀጋ ከሆኑት የአረብ ቤተሰብ የተወለዱ ናቸው ። አባትና እናታቸው በልጅነታቸው በመሞታቸው በአያታቸው እና በአጎታቸው ተንከባካቢነት ያደጉ ናቸው። በልጅነታቸው ታማኙ በሚል ቅጽል ስም ይጠሩ ነበር ። በመልካም ባሕሪያቸው በለሰላስነታቸው በሐቀኝነታቸውና በደግነታቸው ሰዎች በጣም ይወዷቸው ነበር ። በልጅነታቸው የቁረይሽ በግ ጠባቂ በመሆንና በኋላም በመካ ከበርቴዋ ሴት ለከድጃ የንግዳቸው የስራ መሪ በመሆን ሰርተዋል ። በኋላም 25 ዓመት ሲሆናቸው ከድጃን አገቡ ። እመት ከድጃ የነብዩ መሐመድ ብቸኛ ሚስት ነበሩ ። ከድጃ ለነብዩ መሐመድ የቅርብ ረዳት ታማኝ ሴት ነበሩ ። በመንፈሳዊ ዕድገትም ሆነ በኢኮኖሚ በ23 ዓመት የነብይነት ተልዕኳቸው ከፍተኛ ድጋፍ ያደርጉላቸው ነበር ።

ነብዩ መሐመድ የነብይነት ተልዕኮ የተቀበሉት በ40 ዓመታቸው ነበር ። ሒራ በተባለው ዋሻ በጃበል አል ኑር (በመካ በሚገኘው የብርሃን ተራራ ተብሎ በሚጠራው)

በመቀመጥ ማድረግ የሚገባቸውን ሲያብሰለስሉ በነበሩበት ሁኔታ ረጀብ 27 መልአኩ ገብርኤል (ጅብሪል) በመውረድ የመጀመሪያውን የቁርአንን ጥቅስ አነበበላቸው ። አንብብ በፈጠረህ አምላክ (ጌታ) ስም አላቸው ። የሰውን ልጅ ከረጋ ደም በፈጠረው ጌታ ስም አንብብ አምላክህ ብጤ የሌለው የተከበረ በሆነው፤ አለ ጅብሪል ።

> « አንብብ በዚያ (ሁሉም) በፈጠረው
> ጌታህ ስም፣ሰውን ከረጋ ደም በፈጠረው
> (ጌታህ ስም) አንብብ ጌታህ በጣም ቸር
> ሲኾን »

(ቅ.ቁ 96፡1-3)

ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ነብዩ ወደ ሌላ የሕይወት ምዕራፍ ተሻገሩ ወደ ነብይነት ደረጃ ዘለቁ ። በመካ ለ13 ዓመታት የአላህን አንድነት አስተማሩ ። ጣኦት አምላኪዎችንንና አጋሪዎችን አወገዙ፤ ቁርአንን መሰረት በማድረግ ከሙሽሪኮች ጋር ተከራከሩ ሆኖም ፍትሃዊ ባልነበረው የቁረይሾች ሥርዓት ተንገላቱ ። ነብዩ ግን ሁሉን መከራና ስቃይ በመቋቋም ለአላህ አንድነት ታገሉ ። ሰሐባዎቻቸውና እሳቸው በአቡጣሊብ ቋራ መተላለፊያ ተከበው በጣም ብዙ ችግር አሳልፈዋል ። ነብዩ በዚህ 13 ዓመት የትግል ዘመን ወደ ኢስላም ያመጧቸውን ነፃ ያወጧቸውን ሕዝቦች ይዘው

ኢስላማዊ መንግስት ምስረታ ጀመሩ። በመካ የነበረው የትግል ሕይወታቸው በድብቅና በይፋ የሚካሄድ የዲን (የሐይማኖት) ትግል ነበር ።

የሙስሊሙ ቁጥር ከጊዜ ወደ ጊዜ እየጨመረ ሲመጣ ሃይሉም በዚያው ልክ እየተጠናከረ ሄደ ። በዚህ ወቅት የቁረይሽ ባለአባቶች ነብዩን በመደለያ (በጉቦ) መልክ ከጀመሩት ተግባር እንዲገቱ ተማፀኑ ። የቁረይሽ ጎሳ መሪ እንዲሆኑም ጠየቋቸው ። ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ግን ሁሉንም አልተቀበሏቸውም ። በዚህ ሁኔታ የተበሳጬት ቁረይሽዎች ነብዩን በመኝታቸው እንዳሉ ለመግደል ወሰኑ ። አላህ (ሱ.ወ) ይህን የቁረይሽዎች እቅድ አሳወቃቸው ። በዚህ ምክኒያት ወደ የስሪብ እንዲሸሹ ታዘዙ። በዚያች አደገኛ ሌሊት አሊ (ዐ.ሰ) በነብዩ አልጋ ላይ ተኝተው ነበር ።

ነብዩና አቡበከር መካን ለቀው ወደ የስሪብ ቸኳዙ ። በዚህ ጊዜ የስሪብ ከመድረሳቸው ሦስት ቀናት በፊት በአንድ ዋሻ አሳለፉ ። የዚህ ዋሻ መግቢያ በሸረሪት ድር በአላህ ፈቃድ የተሸፈነ ሲሆን ፊት ለፊት የበቀለው የግራር ዛፍ ደግሞ የወፎች ጎጆ ተሰርቶበት ነበር ። በመሆኑም ሰው ያረፈበት ዋሻ አይመስልም ነበር ። በኋላም የስሪብ እንደገቡ ነብዩ በዚያው ለመቆየት ወሰኑ ። ከዚህ በኋላ የስሪብ መዲነት አል ነብይ (የነብዩ ከተማ) ተብላ ተሰየመች ። ነብዩ በመጀመሪያ ደረጃ የሰሩት ነገር መስጀድ መገንባት ነበር ይህ

መስጅድ የነብዩ መስጅድ ተብሎ ተሰየመ። የመጀመሪያውን የኢስላም ህብረተሰብ በዚሁ ከተማ መሰረቱ። ይህ ህብረተሰብ በፍትህ በፀጥታና በነፃነት መርህዎች የተመሰረተ ኢስላማዊ ህብረተሰብ ነበር ። በመዲና የ11 ዓመት ቆይታቸው ከሙሽሪኮች ጋር በብዙ የጦር ሜዳዎች ተዋግተዋል ። ከወራሪዎችና ከዕብሪተኞች ከአይሁዶች (ስምምነታቸውን ካፈረሱ ጋር) ተዋግተዋል ። በነዚህ ዓመታት ብዙ የቁርአን አንቀጾች ወርደዋል ። ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ዳኛ፣የጦር መሪ እና ሕዝብ አስተዳዳሪ ሆነው ማህበራዊና ፓለቲካዊ ጉዳዮችን ተግባራዊ አድርገዋል። በመላው አረቢያ ኢስላማዊ እምነትን ሲያስፋፉ ዋናው ማዕከል መዲና ነበረች ነብዩ ወደ መካ የተመለሱት በድል ሲሆን ጊዜውም ከመሞታቸው አንድ ዓመት በፊት ነበር ። ነብዩ መካ እንደገቡ ያን ሁሉ ስቃይና መከራቸውን ለአሳህ ብለው በመተው ለሁሉም አመጸኛ ምህረት ሰጡ ። ይቅር ባይ ነብይ መሆናቸውን አረጋገጡ ። እንዲህ የሙስሊሙ ቁጥር በዝቶ ወታደራዊና ማህበራዊ አቋሙ ጠንክሮ ባለበት ሁኔታ የበላይነትን ለማሳየት አልሞከሩም ። ይቅርታና ምህረትን አስቀደሙ። በዚህ ምክኒያት በመላ አረቢያ ሰላምና መረጋጋት ተፈጠረ፤ ሁሉም ለኢስላም ተንበረከከ፤ በእምነት በፍቅር ተሳሰረ ።

# ምዕራፍ 4

# ሁለት የእስልምና ገጽታዎች

## 4.1 ሸሪአ (ኢስላማዊ ህግ ወይም ደንብ)

ኢስላም የተለያዩ ትምህርቶችን ያጠቃልላል ። እነዚህም

1. የሸሪአ፣ወደ ፈጣሪ የሚያስጠጋ የፀሎት ዓይነት፣
2. ፍልስፍና የሞራልና የታሪክ ወዘተ ናቸው ።

ኢስላማዊ ህግና ደንብ ሸሪአ ተብሎ ይታወቃል ። ሸሪአ የአላህ ትዕዛዝ ተግባራዊ የሚሆንበት (አድርግ ወይም አታድርግ) በሚል ትዕዛዝ የሰው ልጅ የተፈቀዱና የተከለከሉ

ነገሮች የሚማርበት የሕግ መስክ ነው ። የአላህን ትዕዛዛት ከሰው ልጅ ፍላጎት ጋር በማያያዝ የሚገለጽበት አግባብ ሽሪአ ይባላል ። የሰው ልጆች አላህ በሚያዘው መሰረት የሕይወት መስመራቸውን ያስተካክላሉ ። ሙስሊሞች ሥራና፣ አትሥራ የተባሉትን አውቀው በሕይወት ዘመናቸው በትክክል የፈፀሙ ለዘላለማዊ ቤታቸው ሁኔታዎችን ያመቻቹ ሲሆን በሕይወት ዘመናቸውም የሐሴት ባለቤት መሆን ይችላሉ።

መለኮታዊ ትዕዛዝ ከሰው ልጅ ፍላጎት ጋር አብሮ ተጣምሮ የሚሄድ ሲሆን እንደ ሙስሊም ደግሞ የግልም ሆነ የማህበረሰብ ተግባር በፍፁም ከመለኮታዊ ትዕዛዝ ውጭ ሊሆን አይችልም ። በሽሪአ የተመራ ሕይወት የተደራጀ፣ የሰመረ እና የተቀደሰ እንደሚሆን የተረጋገጠ ነው ። ሽሪአን ተግባራዊ ማድረግና የአላህን ድጋፍ ማግኘት መነሻ ሲሆን፤ እንደ ሙስሊም ግን ከሽሪአ በተጨማሪ ወደ መንፈሳዊ መስመር (ማለፊያ) መግባት መቻል ይኖርበታል ። ይህ መሥመር ጠሪቃ ሲሆን ወደ እውነት የሚያደርስ መንገድ ነው ።

የኢስላማዊ ልምድና ባህልን አመሳስለን ለመግለጽ ያህል፤ ኢስላማዊ ባህል የአንድ ክብ ነገር መጠነ ዙሪያ ቢሆን ሽሪአ የክቡ ነገር ወይም መጠን ዙሪያ ድንበር ነው ። ይህን ድንበር ማንም መጣስ አይኖርበትም ጠሪቃህ ደግሞ

ሬዲየሱ ነው ። ይህ ሬዲየስ ከነጥቦች ጋር እንደሚያገናኝ ሁሉ እውነትም የሁሉ ነገር ማዕከል ነች ። ከመጠነ ዙሪያው ወደ መሃለኛዋ ነጥብ ያለውን ተመሳሳይ ርቀት ጠብቆ የሚያይዝ ነው።

ሸሪዐ ሸርዕ ከሚለው አረበኛ ቃል የተመሰረተ ሲሆን ይህ መንገድ ማለት ነው። ስለዚህ ሸሪአ ማንኛውም ሙስሊም በሕይወት ዘመኑ የሚጓዝበት የዚህኛውም ሆነ የወዲያኛው ዓለም ደስታና ስኬት መዳረሻ ነው ። የሸሪአ ትዕዛዝ (ሕግ) በሁለት (2) ዋና ክፍሎች ተከፍሏል ። እነርሱም ፡-

1. ኢባዳ (አላህን ለመገዛት የሚከናወን ሐይማኖታዊ ሥርዓት) ኢባዳ ግዴታ የሆነ (ዋጅብ) ወይም ደግሞ የተወደደ (ሙስተሃብ) ሊሆን ይችላል ። ግዴታ ከሆኑት ውስጥ ሰላት (ስግደት) ፣ ጾም፣ ዘካት. . . ወዘተ
2. በሁለተኛ ደግሞ ኮንትራት ውል ወይም ስምምነት ነው ። ይህ ሞአመላት ተብሎ ይጠራል። የፍታብሔር እና የወንጀለኛ መቅጫ ህግን ያካተተ ሲሆን ፓለቲካዊ ፣ኢኮኖሚያዊ ወይም ማህበራዊ ውሎችን የሚጨምር ነው ።

የአላህን ሕግና ትዕዛዝ መከተል (መፈፀም) አንዳንዶቹ እንደሚሉት ነፃነትን የሚጋፋ አይደለም ። በጣም ብዙ የሰው ልጅ ባሕሪያት የተፈቀዱ ናቸው ። ነገር ግን ሁሉም የሰው ልጆች ባህሪ ለፈጣሪ መልካም ሊሆን አይችልም። በመሆኑም በመለኮታዊ ሕግና ትዕዛዝ ሥር ታርቀው መሄድ ይኖርባቸዋል ። ፈጣሪ በፈቀደላቸው ክልሎች ውስጥ የሰው ልጅ ጥበቡንና እውቀቱን ለማስፋትና ለማጠናከር መስራት ይችላል ።

መለኮታዊ ህግጋት (ሸሪአ) ሥርዓትና ድንበር ያለው ቢሆንም ነገር ግን የሰው ልጆችን የመምረጥ ነፃነት አልገደበም ። እንደ ሁኔታው ከተፈቀደለት ሥርዓትና ደንቦች ውስጥ የመጠቀም ነፃነቱን አስፍቶታል። በኢስላም በሸሪአ ማዕቀፍ ውስጥ ያሉት ሁሉ የሰው ልጅ በሕይወት ዘመኑ ሊያጋጥመው የሚችሉትን ሁሉ በአግባቡ ይገለገልባቸው ዘንድ ጥበብና እውቀት ሰጥቶታል ።

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በሕይወት ዘመናቸው ያደርጉት የነበረው፣ያዘወትሩት የነበረውን በአንፃሩም ያላደረጉትን ወይም የከለከሉትን በአጠቃላይ ሱናቸውን በመከተል እስከ ወዲያኛው ጠብቆት ሊቆይ ይገደዳል። በቁርአን ውስጥ በጥቅሉ የተቀመጡትን በዝርዝርና በአሰራር ደረጃ የሚያስቀምጠው የነብዩ ሐዲስ ነው ።

ሺአዎች ከነብዩ ሱና በተጨማሪ የኢማሞችን ልምድና ባህል በተጨማሪ ይጠቀማሉ ፡፡ ይህን መሰል ተጋድሎ አጅቲሃድ ይሉታል፡፡ ከሸሪአ ሕግ ቀጥሎ ሙስሊሞች በሁለተኛ ደረጃ አጥብቀው የሚከተሉትና የሚከታተሉት ነገር ቢኖር የነብዩ ሱና ነው ፡፡

ኢማም ጃአፋር ሳዲቅ ከነብዩ የዘር ሐረግ በቅርበት የሚገኙት (አህሉልበይት) በሁለተኛው መቶ ዓ.ሂ ይኖር የነበሩት ግለሰብ ፍቅህ ኢ-ጃፋሪ የተባለውን አስተምህሮት አስፋፉ ፡፡ አኒህ ሰው የሻሪአ ህግ ታዋቂ መምህር ነበሩ ፡፡ በኢራን፣በኢራቅ እና በሊባኖስ የሚኖሩ ሺአዎች የኢማም ጃአፋር አስተምህሮት (የሸሪአ ሕግ) ተከታዮች ናቸው ፡፡

ሱኒዎች አራት ዋና ዋና የሕግ ት/ቤቶች (መዛሃቦች) አሏቸው ፡፡ እነሱም ፡-

1. ***ማሊኪይ*** ፡- በማሊክ ኢብን አነስ የተመሰረተ ሲሆን፤ በሰሜን ምዕራብ ያሉ ሕዝቦች ይህን አስተምህሮት (ሕግ) ይከተላሉ ፡፡
2. **ሐንበልይ** ፡- በአህመድ ኢብን ሐምበል የተመሰረተ ሲሆን በሶሪያና በሳውዲ አረቢያ ሙስሊሞች በብዛት የሚተገበር የአስተምህሮት ዓይነት ነው፡፡
3. ***ሻፊኢይ***፡- በኢማም ሞሐመድ ኢብን ኢድሪስ ሻፊኢ የተቋቋመ ት/ቤት (አስተምህሮ) ሲሆን፤

በጣም ብዙ የሙስሊሙ ዓለም የሚከተለው ት/ቤት ወይም አስተሳሰብ ነው ። በግብጽና በደቡብ ምስራቅ ኤስያ ያሉ ሙስሊሞች የዚህ መዝሃብ ተከታዮች ናቸው ።

4. **ሐነፊይ ት/ቤት፡-** በአቡ ሐኒፋ የኢማም ሳዲቅ ቀጥተኛ ተማሪ በነበሩ ሽህ የተቋቋመ ነው ። ይህን መዝሃብ የቱርክ እና የታችኛው ክፍለ ዓለም ሙስሊም ሕዝቦች በብዛት ይከተሉታል ።

ቀደም ሲል ለመግለጽ እንደሞከርነው ። የሸሪአ ሕግ በኢባዳና በሞአመላት (የልውውጥ ሕግ) ተብሎ ይከፋፈላል ግዴታ የሆኑት ሰውን ከፈጣሪው ጋር የሚያገናኙት ትዕዛዛት ሲሆኑ ተዘወትው የሚከናወኑ የሐይማኖት ሥርዓት ናቸው። በሌላ በኩል ደግሞ ሞአመላት የሚባሉት ማህበራዊና ግላዊ የሆኑ ተግባራትን ከሸሪአ ሕግ አንፃር ማከናወን ነው ።

በአራቱ የመዝሐብ ኢማሞች አስተምህሮት ዙሪያ የተወሰኑ ልዩነቶች ተስተናግደዋል ። ቢሆንም ግን ልዩነቱ መሰረታዊ አይደለም ። በቀን አምስት ጊዜ መስገድ (17 ረካአት) የጁምዓ፣የፈጥር ስግደቶች እና ሌሎች ሶላቶች የመሬት መንቀጥቀጥ፣የጎርፍና የፀሐይ ግርዶሽ በሚፈጠርበት ጊዜ የሚሰገዱ ስግደቶች ኢስላም በሚያዘው መሰረት ይከናወናሉ ።

ኢስላማዊ የሕግ ሥነጹሑፍ የረመዳን ወር ጾም እና ሌሎችን በተመለከተ በሰፊው የሚተነተኑ ይሆናል ፡፡ ጾም ግዴታ የሆነ መላው ሙስሊም ዕድሜው የደረሰና ጤናማ የሆነ (አእምሮው የተደላደለ) የሚጾመው ነው ፡፡

በጾም ወቅት ጾመኛው ከምግብና ከመጠጥ (ውሃ) ተከልክሎ ሙሉ ቀን የሚውል ሲሆን በተጨማሪም ጾሙን ከሚያፈርሱ አልባሌ ነገሮች ሁሉ ይከለከላል ፡፡ በአጠቃላይ ሥጋዊ ፍላጎታቸውን በሙሉ ተቆጣጥረው እስከ ጾም መፍቻ (ማፍጠሪያ) ሰዓት ይቆያሉ፡፡ በጠና የታመመ ሙስሊምና መንገደኛ የሆነ ሙስሊም የረመዳንን ወር እስኪድን ወይም ካሰበበት እስኪደርስ ላይጾም ይችላል ፡፡ ነገር ግን በኋላ የታመመው ከተሻለው መንገደኛውም ካሰበበት ከደረሰ በኋላ ጾሙን መቀጠል ይኖርበታል ፡፡ ያልጾማቸውን ቀናት መጾም ይገባዋል ፡፡

አንድ ሙስሊም ጾመኛ ከምግብና ከውሃ ተከልክሎ መዋሉ ሳይሆን ቁምነገሩ በተጨማሪም ምላሱን፣ዐይኑንና ጆሮውን ሐጢአት ከሚሆኑ ነገሮች መጠበቅ ይገባዋል፡፡ መላ አካሉ መጾም መቻል ይኖርበታል ፡፡ አላህ (ሱ.ወ) ወሳኝ የሆነችውን ሌሊት (ለይለቱል ቀድር) ሊገጥመው ስለሚችል የረመዳንንም ሌሊት በኢባዳ ሊያሳልፍ ይገባዋል ፡፡

## 4.2 ጠሪቃህ (መንፈሳዊ መንገድ)

ኢስላም ሕይወት የሌለው ወይም ደረቅ ሐይማኖት አይደለም። አርግ አታድርግ በሚሉ የሸሪአ ሕጎች ዙሪያ ብቻ ያተኮረ ሳይሆን ሌሎችንም ሥርዓት ባህሎች መንፈሳዊ ሥርዓትና በቀጥታ ወደ ፈጣሪ የሚያስጠጉ የፀሎት ሥርዓቶች አሉት ። ኢስላማዊ እውቀት እንደሚያረጋግጥልን አላህን እንደሚያይህ እንደምታየውና ከእርሱ ጋር በቅርብ እንዳለህ አድርገህ በመገመትና በማመን ፀሎትና ንግግርህን በማድረግ የመንፈስ ርካታ ከማግኘትም በተጨማሪ የፀና ሕይወት መፍጠር ትችላለህ ። የኢስላም መንፈሳዊ አስተምህሮት መሰረቱን ከቅዱስ ቁርአን ያደረገ በመሆኑና የነብዩንም ሱና ስለሚጨምር ኢስላም እንደ መለኮታዊ ሐይማኖት ጣፋጭና ሕይወት ያለው እምነት ነው ።

የጥንት ሙስሊሞች ወይም በቀደምት የኢስላም ዘመናት እንዲህ ዓይነቱ ሁኔታ ጠሪቃህ ይባላል ። ወይም ተሰውፍ ይባላል ። ይህ በቀጥታ ከአላህ ጋር በፀሎት ለመቀራረብ የሚደረግ ጥረት በሁለተኛው መቶ ዓ.ሂ በሱፊዎች ይዘወተር የነበረ ነው። አሁንም ቢሆን የዚህ አስተሳሰብ ያላቸው አይጠፉም ። ኢስላም ራስን አግልሎ በብቸኝነት የሚካሄድን ገዳማዊ የሕይወት ዘይቤ ላይ የሚወሰን አይደለም። የሸሪአን ሕግ በማይዳፈር መልኩ ወደ ፈጣሪ የሚደረግ መንፈሳዊ ጉዞ በአላህ ተቀባይነት ያለው ለመሆኑ ኢስላማዊ አስተምህሮት ያረጋግጥልናል። ይህም

የፀሎት ሥርዓት ሕያው የሚሆነው የነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) ሱና ስንከተል ብቻ ነው ።

የሱፊ አስተምህሮት ኢስላምን በብዙ መልኩ ያጠናከረ ቢሆንም አንዳንድ መሰረታዊ ትምህርቶቻቸው ከወልዮች አስተሳሰብ ጋር የተቆራኘ ነው ። ይህም የቁርአንን ውስጠ ሚስጥር ተረዳን ብለው በብቸኝነት በሚያምኑትና ወደ አላህ የሚያቀራርባቸው ፀሎት ከብዙሃኑ ሙስሊም አረዳዱ የተለየ ነው ብለው ስለሚገምቱ ነው ። ሺአዎች የወልዮችን አካሄድ እጅግ የሚደግፉ ሲሆን በተለይም ደግሞ “ ከስህተት የፀዱ ” የሚላቸውን ኢማሞች በአጠቃላይ እና ኢማም አሊንና ኢማም ሳዲቅን በተለይ የቁርአንን ውስጣዊ ምስጢር አዋቂ አድርገው ያምኑባቸዋል ። በመሆኑም የእነሱ ተፍሲር ወደር የለውም ይላሉ ።

ኢስላም መንፈሳዊ ትምህርት ወደ አላህ የሚደረግ ፀሎት ወደ አላህ በፍቅር በመቅረብ የፀሎት ሥርዓትን ማከናወን ሲሆን ግዴታ የሆኑትንም ጭምር አብሮ በማካሄድ ነው ። በዚህ ሁኔታ የሚከናወን ፀሎት ለሐይማኖቱ ለዛ ይሰጠዋል ይላሉ ።

ኢስላማዊ ሚስቲስዝም (በጾምና በፀሎት ከአላህ ጋር መገናኘት) ጊዜ የማይሽረውና የተደራጀ ዕቅድ ሲሆን ደረጃ በደረጃ ወደ አላህ የሚያገናኝ መንገድ ነው ። ይህ ዐይነት ፀሎት በአንድ አካል በኩል አላህን ለማስታወስ (ለመዘከር)

የሚጠቅም ሲሆን በተጨማሪ ደግሞ የሥነ ልቦና ዝግጅት በማድረግ ወደ ዘለዓለማዊ ሕይወቱ የሚያደርገውን መሰናዶ የሚያጠናቅቅበትን ሁሉ ያመቻቻል ።

ሁሉም ሙስሊም እና በተለይም በጾምና በፀሎት ከአላህ ጋር መገናኘት ይቻላል የሚሉትም ጭምር የነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) መንገድ መከተል እንዳለባቸው ያምናሉ ። የኋለኞቹ ጥልቀት ባለው ሁኔታ የሚደረግ ፀሎትና ዚክር የአላህን ስም ደጋግሞ መጥራት ለብቃት ያደርሳል ይላሉ ። የሌሊቱ የመንፈስ ጉዞ ለፀሎት አዘውታሪዎች የማይታበል ሐቅ ነው ይላሉ ።

አቡበክርና ኢሊ (ዐ.ሰ) በመንፈሳዊ ጉዞ ረገድ ከነብዩ በኋላ ለውጥ ያመጡ ናቸው ብለው የሚያምኑ ሱፊዎች አሉ ። የሱፊዎችን የዱአ (የፀሎት) ባህልና ሥርዓት ያስቀጠለ ግለሰብ ሐሰን አል -በስሪ ነው ።

በሁለተኛው መቶ ዓ.ሂ የጠሪቃ ተከታይ ሱፊዎች ታዋቂ ከነበሩት ሱፊዎች ዙሪያ በመሰባሰብ መንፈሳዊ አመራር እንደተቀበሉ ያስረዳል ። እነዚህ ሰዎች ከዓለማዊ ነገር በመራቅ ሌሎች ሙስሊሞችንም ከመንደላቀቅ በሽታ እንዲወጡ የበኩላቸውን ጥረት አድርገው ነበር ። ኢስላማዊ ሚስቲይሲዝም ከቡድሃና ከሒንዱ እምነት ፀሎት የተለየ ነው ።

በዘጠነኛው ምዕተ ዓመት (A.D) የሱፊዎች ክበብ በባግዳድ በጣም ተጠናክሮ ነበር ። ለዚህ የሱፊ ቡድን መሪ የነበረው ጁነይድ ባግህያዲ የተባለ ሰው ነው ። በዚህ ቡድን ውስጥ ታቅፎ የነበረው መንሱር አል-ሐላጂ እኔ ነኝ እውነት (አነ አል-ሐቅ) በማለቱ በሙስሊሞች ሊገደል በቅቷል ። በኹራስሳን ከነበሩበት ሱፊዎች ታላቁ ሱፊ ባያዚድ ባስታሚ በጣም ብዙ ተከታዮች ነበሩት ። በ11ኛው ክፍለ ዘመን ታላቁ ሱፊ ተብሎ የሚጠራው አቡ ሙሐመድ አል-ገዛሊ የራሱን የሱፊ መርሆና ደንብ በማዘጋጀት ከሸሪአ ሕግ ተከታዮች ጋር ብዙ ክርክሮችን አድርጎ ነበር ። ከዚህ ጊዜ ጀምሮ የሱፊ አስተሳሰብ መዋቅራዊ ይዘት ተከተለ።

ጠሪቃ (መንፈሳዊ መንገድ) ሦስት ነገሮችን ይዟል ።

1. ስለ ተፈጥሮ ማስተማር

2. ሐቅን (እውነትን) የማግኘት ዘዴ እና

3. ወደ ፈጣሪ የሚያቃርብን መንፈሳዊ ጉዞ ማድረግ የሚያስችልን ትምህርት በመስጠት አይነጥላን ገፎ ፈጣሪን የሚያይበትን ፤በመንፈስ የሚጋልብበትን መገለጫዎች ማሳወቅ።

እነዚህ አስተምህሮዎች መልክና ሥርዓት ይዘው የተቀነባበሩት ሞሐዩዲን ኢብን አረቢ በተባለ ሰው ነው ። ይህ ሰው የሚስቲስዝምን ንድፈ ሐሳብ የመሰረተ አንዱ የሱፊዝም ታላቅ ሰው ነው ።

ሱፊዎች በሂንዱዝምና በፕሌቶይዝም አስተሳሰብ እንዲሁም በሒርሚቲስዝም ፍልስፍና የተማረኩ ሙስሊምች ናቸው ። ሌሎችም ጥቂት ስለ መንፈሳዊ ትምህርት የሚያውቁ ሙስሊሞች ስለ ሥነፈለግ፣ ስለ መላዕክታን፣ ስለ ነፍስ እና ስለ ወዲያኛው ዓለም ዕውቀት ለመስጠት ተንቀሳቅሰው ነበር ። ሁሉም መነሻቸውን ከቁርአን ያደረጉ ቢሆንም በጣም ጥቂቶቹ ነበሩ በአላህ አንድነት ላይ ባተኮረ መልኩ ጥናታቸውን ያካሄዱ የነበሩት። ዝክር (አላህ ማወደስ) ከእውነቱ ለመድረስ የሚያበቃ ነው ይላሉ ። ሁለቱም ቡድኖች በጠሪቃ ሸኮቻቸው አማካይነት ወይም የቅርብ ክትትል ነበር ዘወትር ፀሎታቸውን የሚያከነውኑት።

እነዚህ የተለያዩ አስተሳሰቦች በኢስላም ቦታ ሊኖራቸው የሚችለው ሁሉም ፍልስፍናና ጥበብ ከአላህ አንድነትና ከመለኮታዊ መመሪያ ሸሪአ ካልወጡ ወይም ካላፈነገጡ ብቻ እንደሆነ የኢስላም ምሁራን ይስማማሉ ።

# ምዕራፍ 5

# ኢስላምና ሌሎች ሐይማኖቶች

በቁርአን ዲን (አል-ዲን) ወይም ሐይማኖት የሚጠቀሰው አጠቃላይ በሆነ መልኩ ነው ። ኢስላም የሚለው ደግሞ ሁለመናህን ለአላህ መስጠት አንድነቱንና ሁሉን አድራጊነቱን መቀበል ሲሆን፤ለነብዩ መሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) በቁርአን አማካኝነት የተሰጠ ሃይማኖት ነው ሲሉ ይተረጉሙታል ። ቁርአን ኢብራሂምም ሙስሊም ነው ይላል። በአጠቃላይ ሁኔታው ኢስላም ማለት በአላህ

በመላኢኮች፣ በነብዮች እና በመለኮታዊ መጽሐፍት የሚያምን ሐይማኖት ነው ። የቁርአን አንቀጾች እንደሚያረጋግጡት በየዘመኑ ለነበሩ ሕዝቦች ነብይ ተልኳል። አዳም የመጀመሪያው ነብይ ሲሆን ኢየሱስ እና ሙሴ ደግሞ ቁርአን የሚጠቅሳቸው ታላቅ ነብይ ነበሩ ። መለኮታዊ መጽሐፍ ከፈጣሪያቸው የተሰጣቸው ስለመሆኑ ቁርአን ይናገራል ።

ሙስሊም የሐይማኖት መሪዎች የተለያዩ እምነቶችን በተመለከተ የተላኩትን ነብያት እና አጠቃላይ ሁኔታ ጽፈዋል ። ካጠኑዋቸው ሐይማኖቶች ውስጥ የይሁዳ፣ ክርስትና፣ዘሮአስተሪያንስ፣ሳቢያንስ (ኮከብ አምላኪዎች) ወዘተ ነበሩ ። ይህ የሚያመለክተው ኢስላም በሐይማኖቶች መካከል መቻቻልና መከባበር መኖር እንዳለበት ስለሚያምን ነው ። መለኮታዊ የሆኑ ሐይማኖቶች፣በቅዱስ ቁርአን በብዙ አንቀጾች ተጠቅሰዋል። ከነሱም ውጭ ያሉ ሐይማኖቶች የሚገኙባቸው ሙስሊም ሀገሮች የአማንያን ነፃነት ጠብቀው እና አክብረው እንደሚይዟቸው ተጨባጭ የሆኑ ማስረጃዎች አሉ። ኢስላማዊ ታሪክና ፍልስፍና እንዲሁ፣ የእምነቱ ቀኖና የሌሎች ሐይማኖቶች ግንኙነትና የአማኞችን ሁኔታ በተመለከተ የሚያስረዱ በቂ ሰነዶች አሉት። በተለይ ደግሞ በኢራን ህንድ ቻይና እና እስፔን ሙስሊሙ ህዝብ ከሌሎች

አማኞች ጋር መልካም መስተጋብር ፈጥሮ በመኖር ላይ እንዳለ የወቅቱ ገሀድ ሐቅ ነው ፡፡

ኢስላማዊ ሸሪአ ሙስሊሙ ህብረተሰብ የመፅሐፍት ባለቤት የሆኑትን ተንከባከቡ፤ የእነሱንም የሐይማኖት ህግ አክብሩ፤ ይላል፡፡ ምንም እንኳን ባሁኑ ዘመን የተለያዩ አስተሳሰቦችና አመለካከቶች የተለያዩ አገሮችን ህዝብ አመለካከት የሚቀይሩ ሁኔታዎች ቢኖሩም ኢስላም የቁርአንን ትዕዛዝ አጥብቆ ስለሚያከብር የተፈጠሩትን ሁኔታዎች መቋቋም ችሎአል ፡፡ በመሆኑም ኢስላማዊ ስልጣኔ በደረሰበት ደረጃ የሚገኙ የሌላ ሀይማኖት አማኞችን ፍትሐዊ በሆነ መንገድ ይዞአቸዋል፡፡ ለምሳሌ የኦርቶዶክስ ቤተክርስቲያን መዕከል አሁንም ቢሆን በጥንት ቦታው በኢስታንቡል ይገኛል ፡፡ ቁጥራቸው በጣም ብዙ የሆነ አርመናዊያን በኢራቅና በኢራን ይገኛሉ ፡፡ የዩህዳዊያን የምርምርና የሌላ ጥናት ስራዎች በአረበኛ ቋንቋ ተዘጋጅተው በእስፔን ይገኛሉ፡፡ እስፔን በሙስሊሞች ግዛት ስር በነበረችበት ግዜ ይህን የዩህዳዊያን ሰነድ ማስቀመጥ ምን ያህል ኢስላም ፍትሐዊ የሆነ ሐይማኖት እንደሆነ ያረጋግጣል ፡፡ ሙስሊሞች ካላቱን እስፔን በ1492 ዓመተ ዓለም ተጠርገው ሲወጡ ቅርስና ታሪካቸውን ለመጠበቅ ሲሉ ወደ ሙስሊም ሀገሮች ጥገኝነት አልጠየቁም፡፡ ነገር ግን ያደረጉት ነገር ከኢስላማዊ መርህ አንፃር ተቻችሎ መኖር

የሚለውን መመሪያ በመከተል እስፔናዊያን ሙስሊሞች ሀገራቸው ውስጥ መኖር መርጠዋል ። ይህ በሰላም አብሮ መኖር የሚለው የኢስላማዊ መመሪያ በግልጽ የሚታይባት ሀገር ህንድን ስንመለከት ሙስሊሙና ሂንዱው አብረው በሰላም ይኖ'ራሉ። በሌሎችም ሀገሮች በተመሳሳይ በዚሁ ሁኔታ የሚኖሩ ሙስሊሞች በጣም ብዙ ናቸው ።

እንደ ኢንዶኔሲያና ናይጀሪያ የመሳሰሉ ሀገሮች ሚሺኒሪዎች ተስማምቶ የሚኖረውንን ህዝብ ሲበጠብጡት ይታያል። ተገቢ ባልሆነ ዕብለታቸው ምክንያት ሃይማኖትን ከሀይማኖት ጋር በማጋጨት ወደ አልተፈለገ ፓለቲካዊ ስጋትና ባህላዊ ግጭት ለመቀስቀስ የነፃነት ጥያቄን ሊያስነሳ ችሎአል ። በሶቭየት ህብረት እና በምስራቅ አውሮፓ በቦስንያና ኸርዚ ጎቪና የተቀሰቀሰውን አይነት የመከፋፈልና የመበታተን ብሎም የከፋ ጦርነት የሚያስከትሉት ሁኔታዎች ተፈጥረዋል ። የእስራኤል መንግስት ከተመሰረተ ጀምሮ በአረቦችና በእስራኤሎች መካከል የማይበርድ ግጭት ተፈጥሮአል ። ይህ ግጭት በሙስሊሞችና በዩሀዳውያን መካከል ግን አይደለም ምክንያቱም የፍልስጤም ክርስቲያንና ሙስሊሞች አንድ በመሆን በነፃነታቸው በእስራኤል ላይ ተነስተዋል። አረብ ያልሆኑ ሙስሊሞች የፍልስጤምን የነፃነት ጥያቄ ከፍትሐዊነት አንፃር ቢደግፉትም ነገር ግን የእስራኤል ደጋፊ ያልሆኑትን ዩሀዶች በጭፍን

አይቃወሙም። ከሁለት አስርት አመታት በፊት የተጀመረው የፍልስጤምን የነፃነት ትግል ማገዝ (መርዳት) አሁንም ቢሆን ብዙ ሙስሊም ሀገሮች በይፋ የደገፉት አይደለም ።

## ምዕራፍ 6

## በሙስሊሙ አለም አዲስ የእድገት አቅጣጫ

በ13ኛው መቶ ዓ.ዒ ሙስሊሙ ህዝብ የአውፓውያንን ሴራና የበላይነት ኢስላም እየደረሰበት ያለውን ግፍ መገንዘብ የቻሉ በጣም ጥቂት ሙስሊም ሀገሮች ናቸው። ይህን የአውሮፓውያንን ተጽእኖ ለመቋቋም ይችሉ ዘንድ ራሳቸውን ያስተካከሉ (በመንግስታቸው ውስጥ ለውጥ ያመጡ)

ሙስሊም ሀገሮች በጣት የሚቆጠሩ ናቸው። ህዳሴአቸው ኢስላም መቆየት ፋይዳ ያለው ነው በአቶማን ግዛት የተሸሻለው የሀገሪቱ መንግስት ዋና አላማው ኢራንንና ሌሎች ሙስሊም ሀገሮችን ጠራርገው ከሀገራቸው በማስወጣት ነበር ሰይድ ጀማል አልዲን አሳዳባዲ (ሰይድ አፍጋኒ ተብሎ የሚታወቀው ታላቁ የሙስሊም ተሀድሶ አምጭ ሲሆን ይህ ሰው ሙስሊሙን ህዝብ ለህዳሴ ማንቀሳቀስ እና አንድነቱን መፍጠር የጀመረው ከምዕራባውያን የረጅም ግዜ አላማና አቅጣጫ አንፃር ነበር። በግብፅ ጥቂት ምሁራን እንደ ሙሐመድ አብዱ (የሰይድ ጀማል ተማሪ የነበረ) ዘመናዊ ህዳሴውን በአግባቡ በመረዳት ኢስላማዊ ትምህርት ዘመናዊ በሆነ መንገድ እንዲደራጅና ሙስሊሙ ህብረተሰብ በትምህርት እንዲታነፅ ከፍተኛ ጥረት አድርጎአል። በወቅቱ በህንድ የነበሩ ሙስሊሞች በተመሳሳይ ሁኔታ ኢስላማዊ ስልጣኔው ከዘመናዊ ትምህርት ጎን ለጎን የሚያድግበትን መንገድ አመቻችተው ነበር። ለመጀመሪያ ግዜ በሙስሊ ኣለም ኢራን በ1323 ዓ.ሂ ፓርላማ አቋቋመች። ይህ የሆነው ህገ- መንግስታዊ ንቅናቄ በአውሮፓውያን አስተሳሰብ አማካኝነት የተፈጠረ ነው ።

ተመሳሳይ ንቅናቄዎች በ20ኛው መቶ ክፍለ ዘመን በፈጠሩት ሁኔታ ልማትና እድገት መታየት ጀመረ። መሐመድ ኢቅባል የተባለ ሰው እንቅስቃሴ በመፍጠር

ፓኪስታንን ነፃ ኢስላማዊ ሀገር እንድትሆን መንገድ ከፈተ። መሐመድ ኢቅባል ዛሬም ድረስ በብዙ ሙስሊም ሙህራን የንቅናቄ እና የነፃነት ፋና ወጊ ሆኖ ይታያል። ካለፉት ጥቂት አሥርተ አመታት ወዲህ በሙስሊም አክራሪዎችና ተሀድሶ መሪዎች መካከል የሐሳብ ልዩነት ተፈጥሮአል። ይህም ጥንታዊና መሰረታዊ የሆነው አስተሳሰብ አዲስና አዳጊ ከሆነው አስተሳሰብ ጋር በሀይማኖቱ ዙሪያ ልዩነት ተፈጥሮአል። ምንም እንኳን የተሀድሶ አቀንቃኞች በያዙት አቋም መጠቀም ቢፈልጉም እያደገ የመጣው አዲስ አስተሳሰብ በተፈጥሮአዊ ሁኔታ ሊሽራቸው በቅቶአል። በኢራን የተካሄደው ኢስላማዊ አብዮት በአያቶላህ ኾመይኒ አመራር አድሀሪውን የፓህላቪ ግዛት በመጣል ያሁኑን የኢስላማዊ መንግስት ናሙና ኢስላማዊ የፓለቲካ እምነት አስፍኗአል ።

በተለያዩ የአለም ክፍል የሚገኙ ሙስሊም ምሁራን ተጨባጭ በሆነው የአለም ሁኔታ ምክንያት የሚገጥሟቸውን ፈተናዎች ለማለፍ የሚያስችል ንድፈ ሐሳባዊ መርህ እና ቅኝቶችን በማዘጋጀት ኢስላም የያዘውን የእድገት አቅጣጫ ከህዝቡ ፍላጎትና ምኞት ጋር ተጣጥሞ ለዘመናት እንዲቀጥል ጥረት በማድረግ ላይ ይገኛሉ። የወቅቱ መፈክር ከሆነው የዲሞክራሲ ጥያቄ አንፃር ኢስላም ከመሰረቱ ስለ ዲሞክራሲ ያለው እምነትና አመለካከት

እንዲቀጥል በማድረግ ረገድ ኢስላማዊ የሹራ ባህል (መመካከር) እና ባያህ( ሽንጎ) የመሳሰሉትን የመመካከርና የመወያት ባህልን ማዳበር ቀዳሚ ሆኖ አግኝተውታል ።
ዲሞክራሲ መሰረቱ የምእራባውያን ሊበራልሊዝም ሳይሆን ከ1400 መቶ አመት በፊት የሙስሊሙ ባህል ሆኖ የቆየ ነው ።

ሌላው አወዛጋቢ ጉዳይ የሆነው የሴቶች ወይም የሴትነት ጥያቄ ነው። ይህ ጥያቄ ለምእራባውያን አዲስ ክስተት ሆኖ ብቅ ያለው ከ100 አመት ባነሰ ግዜ ውስጥ ነው። ነገር ግን ኢስላም ሲጀመር ጀምሮ የሴቶችን መብት ከማንም መለኮታዊ ሀይማኖት በተለየ መልኩ ሲያስተናግደው የቆየ ነገር ነው። ይህን አጀንዳ አንዳንድ ሙስሊም አሳቢዎች ከምእራባውያን ቅኝት እንፃር ሊመለከቱት ቢችሉም በሙስሊሙ ህብረተሰብ ጥንታዊነት ኢስላምን የሚያውቁ ሰዎች የሚክዱት አይደለም።

ሌላው ጉዳይ የሰብአዊ መብት ጥያቄ ነው። ይህም ቢሆን ኢስላም ከማ[illegible] በተሻለ የሰው ልጆችን መብት ሲጠብቅ ቆይቶአል ።የ[illegible] መብት ቻርተር መሰረታዊ የሆኑትን የሰው ልጆች መብት ለሁሉም ቀለም ባህል እና ሐይማኖት ሳይለይ [illegible]ግኅል። ይህ የተባበሩት መንግስታት ድንጋጌ በኢስላምም ከሸሪአ አንፃር ሳይገመገም በጭፍኑ ተግባራዊ

ሊደረግ አይችልም። በቁዱስ ቁርአን የሰው ልጆች መብት በተለያዩ አንቀጾች ተጠቅሶአል ።

ሌላው ፈታኝ ጉዳይ የሆነው የተለያዩ ሐይማኖቶች መኖር ነው ። ሙስሊም ምሁራን (አሳቢዎች) ይህን ክስተት በተመለከተ ንድፈ ሃሳባዊና ተግባራዊ መፍትሔ ለመፈለግ የተቻላቸውን ሁሉ አድርገዋል ። በተለያዩ ሐይማኖት ተከታዩች መካከል መቻቻልና መግባባት እንዲኖር አበረታትተዋል ። ሌላው ችግርና ፈታኝ የሆነው ነገር የምእራባዊያን ባሕል የሙስሊሙን ባሕል መውረሩ ነው ። ይህ ተጨባጭ ችግር ከምን እንፃር መገታት እንዳለበት ሙስሊም አሳቢዎች የተቻላቸውን ሁሉ በማድረግ ላይ ናቸው ።

በአጠቃላይ መሰረታዊ ለውጥ ለማምጣት ሙስሊም አሳቢዎች የተሻለ ዘዴና ስልት መንደፍ፤እንዲሁም ተስማሚ መፍትሔ መሻት ይኖርባቸዋል ።

## ማጣቀሻ መጽሐፍት (Sources Consulted)


- The holy Qur'an.
- Ali ibn Abi Talib. Nahj al-Balagha.
- Bihishti, M.; Bahunar, M.; & Ghafuri. Shenakht-I Islam (Knowing Islam). Tehren: Center for propagating Islamic Culture.
- Shari' ati,A. Islamshenasi (Islamology). Tehran: center for publishing Shari'ati's works.
- Nasr,H.A Young Muslim's Guide to the Modern World. Tarh-I Naw Publications : 1375 (1996)
- Motahhari, M. Collections of works.
- Tabataba' 1, M.H al-Mizan fitafsir al-Quran.
- Encylopedia of sji'ism, published In Iran, 9 Vol. 1995
- Bujnurdi, M.K. The Grand Encyclopedia of Islam,1998.
- Sharma, A. our Religions. Harper San Francisco. Pp. 427-532
- Encyclopedia of Islam, Leiden.

## الإستراتيجيات العامة لمؤسسة عصر الظهور

- الحرص على ضمان استقلالية المؤسسة وعدم انضوانها تحت أي تيار سياسي أو حزبي تحاشياً من المحسوبية أو الدخول في إستقطابات المرجعيات الدينية.
- مد جسور التعاون مع كافة الجهات والفعاليات واللجان التي تشاطرها في نفس النشاط والتطلعات وذلك في اطار القواسم المشتركة ونقاط الإلتقاء.
- الإبتعاد عن الصدام والتجريح والإثارات البغيضة وتجنب الإساءة للأديان وتكريس مبدأ التسامح الذي دعا إليه الإسلام.
- التركيز على الشريط الإسلامي كوسيلة فعالة ومؤثرة ومناسبة للعمالة الوافدة.
- عدم الترويج لأي شخصيات دينية أو تيارات سياسية أو اقتحام دهاليز السياسة على أن يكون جُل إهتمام المؤسسة منصب في إتجاه أهدافها الإجتماعية والتبليغية.

## اللغات المتوفرة:

- الإنجليزية - الأندونيسية - الفلبينية - البنغالية - التاميلية - السنهالية - الهندية الأوردوية.

## من نحن؟

مؤسسة إجتماعية تبليغية ترتكز نشاطاتها في دعوة الجاليات الأجنبية إلى الإسلام وفق مدرسة أهل البيت (ع) في إطار منظومة دعوية حضارية وضمن نظام مؤسسي متقن.

## لماذا هذا الإسم (مؤسسة عصر الظهور)؟

لم يقع الإختيار على هذا الإسم من باب حتمية ظهور الإمام المهدي أرواحنا فداه في هذا العصر فإن للـ عز وجل البداء والأمر كله، فلربما تقتضي مشيئة اللـ عز وجل أن يتأخر ظهوره في زمن لاحق لزماننا، ولكن جاءت هذه التسمية من باب الرجاء والتمني والترقب لظهوره الشريف في هذا العصر بعد تراكم علامات الظهور وتسارع وتيرة الأحداث الدالة و (اللـ العالم) على قرب ظهوره المبارك الأمر الذي يشحذ هممنا ويفجر طاقاتنا لنشر الثقافة الإسلامية المستقاة من أهل بيت العصمة (ع).

## لماذا هذه المؤسسة؟

جاءت فكرة إنشاء هذه المؤسسة بعد الشعور بوجود فجوة واسعة لم تردم في مجال تعريف الجاليات الأجنبية بالإسلام وفق مذهب أهل البيت (ع) وتحسس واقع الدعوة الخجول في أوساطنا الإجتماعية والدينية إثر بروز حالة من التراخي في اتجاه حركة ترجمة وطباعة الكتب والإصدارات المنوعة باللغات الأجنبية فضلا عن تقييد حركة الدعوة في مجالات محددة وضيقة لا تنسجم مع حجم التحديات والتطلعات.

## أهداف المؤسسة:

١ - تعريف الجاليات الأجنبية بالإسلام وفق مدرسة أهل البيت (ع).

٢ - تنمية الحس الدعوي والتبليغي لدى العوائل الكويتية وتشجيعهم على دعوة العمالة الوافدة إلى الإسلام.

٣ - تعريف أرباب الأسر بحقوق وواجبات الخادم وتعزيز القيم الإنسانية والأخلاقية بين الخادم والمخدوم.

٤ - الحد من مشكلات العمالة الوافدة الناتجة عن الجهل بالعادات والتقاليد الكويتية.

٥ - تقوية إيمان الشرائح المستضعفة ودرء الشبهات العقائدية عنهم.